# የ አ ር እ ስ ት ማ ው ጫ ።



ለኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን
በቅዱስ መካን
(ኢየሩሳሌም)
ያላት መብት

# የሰነድ ማስረጃዎች ።

በብፁዕ አቡነ ፊልጶስ
በኢየሩሳሌም የኢትዮጵያ ገዳማት ጳጳስ አርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን
ትጋት የተዘጋጀና የታተመ ።

እ. ኢ. አ. ጥቅምት ፲፱፻፶፫ ዓ. ም.
እ. ኤ. አ. ጥቅምት ፲፱፻፷ ዓ. ም.

በኢየሩሳሌም ዳኛና ጠበቃ በነበሩት በጀሚል አይ. ሐቢቢ
ከዓረብኛ ወደ እንግሊዝኛ ተተረጐመ ።

---

በትምህርት ሚኒስቴር አማካይነት በአቶ ገብረሚካኤል ኪዳኔ
ከእንግሊዝኛ ወደ አማርኛ ተተረጐመ ።



ግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ሥዩመ እግዚአብሔር
ንጉሠ ነገሥት ዘኢትዮጵያ ።



ግርማዊት እቴጌ መነን እንተ ይእቲ ወለተ ጊዮርጊስ ።



ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ባስልዮስ ቀዳማዊ ርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት
ወፓትርያርክ ዘኢትዮጵያ ።



አባ ፊልጶስ ጳጳስ ዘገዳማተ ኢትዮጵያ
እለ በኢየሩሳሌም ።

# መ ቅ ድ ም ።

ሰው አንድ መጽሐፍ ወይም ታሪክ በሚጽፍበት ጊዜ ከጻፈው መጽሐፍ በመጀመሪያው ገጽ፤የሐሳቡን መነሻና መድረሻ የሚገልጽ፤እንደዚሁም መጽሐፉን ለምን ጉዳይ ይጠቅማል ብሎ የጀመረው መሆኑን የሚያስረዳ መቅድም ወይም የሐሳብ መግለጫ መጻፍ ይገባዋል። ስለዚህ የግል ጥቅም ወይም ከንቱ ውዳሴ በመሻት ሳይሆን፤በልዑል እግዚአብሔር ፈቃድ በግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ንጉሠ ነገሥት ዘኢትዮጵያ ጥልቅ አስተዋይነትና ክርስቲያናዊ መሪነት፤ በብፁዕ ወቅዱስ ርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት ወፓትርያርክ ዘኢትዮጵያ አቡነ ባስልዮስ መንፈሳዊ ቅብዓት፤ በሃገር ቅድስት በኢየሩሳሌም የሚገኙትን ገዳማተ ኢትዮጵያን ለማስተዳደር ከኢትዮጵያዊት ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ተመርጬ ወደ ኢየሩሳሌም ለጳጳስነት ተግባር በተላክሁ ጊዜ፤ በኢየሩሳሌም በቅዱሳት መካናት በሚገኙት በክርስቲያን ማኅበሮች መካከል የተፈጠረው ስስትና አለመግባባት ባስገኘው የርስ በርስ መጣላትና መነጣጠቅ ተግባር፤ በተለየም ደግሞ የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ለመንፈሳዊው ተግባርዋ ይጠቅሙኛል ብላ የምታምንባቸው የኮፕት ቤተ ክርስቲያን መሪዎች የወዳጅ ጠላት ሆነው፤ በኢትዮጵያውያን ማኅበሮች ላይ በቅዱሳት መካናት ባሉት ገዳሞቻቸውና በንብረታቸው ሁሉ የሠሩትን ግፍና እስከዛሬም ድረስ የሚሠሩትን የጠላትነትና የቅሚያ ሥራቸውን መከላከል ተገቢ በመሆኑና የመልእክቴም ኃላፊነት ስለሚያስገድደኝ ከጥንት ጀምሮ ብዙ ኢትዮጵያውያን የሰበሰቧቸውን ጽሑፎችና አንዳንድ የቅርብ ተመልካቾች የውጭ አገር ሰዎች የጻፏቸውን ታሪኮች በተቻለ መጠን አጠራቅመን አለ አገባብ በግፍ የተወሰደብንን የርስት መብት በሕግ መሠረት እንዲለቀቅልን በመጠየቅ በዘመናችን ላሉት ለጆርዳን መንግሥት ባለሥልጣኖች ያቀረብነውን የጽሑፍ ማስረጃና አባሪ ማመልከቻ ኢትዮጵያዊና ግፍን የማይወድ እውነተኛ ፈራጅ ሕሊና ያለው ሰው ሁሉ ግፉን ይመለከተው ዘንድ ከልዩ ልዩ ቋንቋ ወደ ዓረብኛ ተተርጉሞ ከዓረብ ወደ እንግሊዝኛ፤ ከእንግሊዝኛ ወደ አማርኛ ተተርጉሞ በሦስት ቋንቋ ታትሞ እንዲወጣ አድርጌ አለሁ ።

<u>ኢትዮጵያ ።</u> (ሐተታ) ኢትዮጵያ አገራችን በሥጋዊ ነፃነቷ ሆነ በሃይማኖታዊ ተግባሯ በቅዱሳት መጻሕፍትና በዓለም ታሪክ ላይ ከፍ ያለ የቀደምትነት ዝና ያላት በጣም የምታኮራ ሰላማዊትና ሃይማኖታዊት ሀገር ናት ። ይኸውም ይታወቅ ዘንድ ሀገረ ሰላም የምትባለዋ ኢየሩሳሌም ወደሷ የተላኩትን የነቢያትንም ደም ስታፈስ የኖረች ይዐቀረው የማይባል ኃጢአትና የግፍ ግፍ ተግባር የተፈጸመበት ሀገር መሆኗን የተጻፉት መጻሕፍትና ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም "እነሆ ከጻድቁ ከአቤል ደም ጀምሮ በቤተ

መቅደስና በመሠውያው መካከል እስከገደላችሁት እስከ በራክዩ ልጅ እስከ ዘካርያስ ደም ድረስ በምድር ላይ የፈሰሰው የጻድቅ ደም ሁሉ እንደሚደርስባችሁ እውነት እላችኋለሁ ይህ ሁሉ በዚህ ትውልድ ላይ ይደርሳል ። ኢየሩሳሌም ኢየሩሳሌም ሆይ፣ ነቢያትን የምትገድል ወደርሷ የተላኩትንም የምትወግር„ ሲል ይነግረናል፣ ማቴ፣ ፳፫ ፴፭-፴፮ ። የቀሩትም ዓለማት እንደዚሁ በነቢያትና በሐዋርያት ላይ የፈጸሙትን የደም ማፍሰስ ተግባር ገድለ ሐዋርያት ይነግረናል ።

ሀገራችን ኢትዮጵያ ግን ያንድ ነቢይ ወይም ያንድ ጻድቅ ደም ያልፈሰሰባት ንጽሕትና ቅድስት ሀገር በመሆኗ ሀገረ ሰላም መባል የሚገባት ኢትዮጵያን ነበር ። የኢትዮጵያ ሰላማዊነት ማስረጃ ፤

<u>አንደኛ፡</u> የሳባ ንግሥት የሰሎሞንን ጥበብ ልትረዳ መጣች ተብሎ እንደተጻፈው ሌሎች አገሮች ከጨለማ ወደ ብርሃን ሲመልሷቸው ለጥቅማቸው የሚመጡላቸው ሐዋርያትን የሚገድሉ ሲሆኑ፣ የኢትዮጵያ ንግሥት ሥጋዊና መንፈሳዊ ጥበብን ስመረዳት ስትሽ ከኢትዮጵያ ተነሥታ እስከ ኢየሩሳሌም ድረስ መምጣቷን ፩ ነገሥት ፲ ፩፡ ዜና መዋዕል ካልእ ፱ ፩ ። ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ፤ "ንግሥተ አዜብ በፍርድ ቀን ከዚህ ትውልድ ጋር ተነሥታ ትፋረድበታለች፣ የሰሎሞንን ጥበብ ለመስማት ከምድር ዳር መጥታለችና፣ እነሆም ከሰሎሞን የሚበልጥ ከዚህ አለ„፣ ብሎ ኢትዮጵያ እምነት በጐደለባቸው በሌሎች ሕዝቦች ላይ ትፈርዳለች ሲል አመስግኖ በመለከታዊ ቃል ከፍ አድርጎ በሌላው ዓለም ላይ ፈራጅ ሲያደርጋት ከመስማት የበለጠ ክብርና ቅድስና አይገኝም፣ ማቴ፡ ፲፪ ፵፪ ።።

<u>ሁለተኛ፡</u> ሌላ ዓለማት የወንጌልን የምሥራች ሊያበሥሩዋቸው የተላኩትን ሐዋርያት የምሥራቹን አንቀበልም ብለው እኩሉን በሰይፍ እየገደሉ እኩሉን በእሳት እያቃጠሉ እኩሉን በመስቀል እየሰቀሉ ንጹሕ ደም በማፍሰስ ልዩ ልዩ ግፍ በሚፈጽሙበት ጊዜ ኢትዮጵያ ያንድ ሰው ደም ሳታፈስ የንግሥት ህንደኬ መላክተኛ መስፍን ኢየሩሳሌም ድረስ መጥቶ የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ሥጋ (ሰው) መሆን ሰምቶ የወንጌልን የምሥራች ተቀብሎ በሐዋርያው እጅ ተጠምቆ ያመጣላትን የሐዲስ ኪዳንን እምነት በዘመነ ሐዋርያት መቀበሏን በሐዲስ ኪዳን በመላው ዓለም ዘንድ ሲነበብ ይኖራል፣ የሐ. ሥራ. ፰፡ ፳፮ ።

<u>ሦስተኛ፡</u> ከንግሥት ህንደኬ መላክተኛ መስፍን የተቀበለችውን የወንጌልን እምነት ለመረዳትና የክርስቶስን ሃይማኖት በሀገሯ ላይ ለመዘርጋት፣ ቅዱስ ፍሬ-ምናጦስን ልከ ሥርዓተ ክህነት አምጥታ ምሥጢረ ጥምቀትና ምሥጢረ ቍርባንን አግብታ ትምህርቱን ከሌላ ሳትሻው ራሷን በራሷ በማስተማር የፈጸመችው የሃይማኖት ስብከት መስፋፋት ተግባር፣ ባዕድ ሰው ያልደከመባት፣ ጻማ ባዕድ ያልተቀላቀለባት ሰላማዊት ሀገር ናትና፣ እንደ እውነቱ ሀገረ ሰላም መባል የሚገባት ሀገራችን ኢትዮጵያ ናት ቢባል እውነት ነው እንጂ ራስን ማሞጋገስ አይደለም ።

አራተኛ፣ በላይኛው መሥመር እንደተነገረው ፃማ በዕድ በልተቀላቀለበት ሌላ ነጋሪ ሳትሻ ብሉይ ኪዳንን በንግሥተ ሳባ፥ ሐዲስ ኪዳንን በህንደኬ ንግሥት መላክተኛ ተቀ ብላ ከቆየች በኋላ አራተኛ መቶ ዘመን ሲጀመር ትምህርተ ሃይማኖትንም ከሣቴ ብር ሃን ብላ ከሰየመችው ከቅዱስ ፍሬ-ምናጦስ ስምታ የሐዲስ ኪዳንን ስብከት ከስፋፋች በኋላ ፣ በኢየሱስ ክርስቶስ ሃይማኖት ፍቅር ቅናት የተናደዱ ኢትዮጵያውያን መናንያን ፍቅረ ዓለምን እየጠሉ በሱዳንና በምድረ ግብጽ በረኻውን እያቋረጡ ወደ ቅድስት ሀገር ወደ ኢየሩሳሌም መጥተው በቅዱሳት መከናት ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ሥራ በሠራ ባቸው ሥፍራዎች እየወደቁ እየተነሡ በመላው ዓለማት ፊት ያሳዩትን የሃይማኖት ተጋድሎ ተግባር የተመለከቱ ጐብኝዎች ፣ አንዳንዱ አብሲኒያን ፣ አንዳንዱም ኖቢያን ፣ አንዳንዱም እንዲያን እያሉ እንደዛሬው ዘመን የዓለም ካርታ ባልታወቀበት ጊዜ ፣ የሃይማኖት ፍቅራቸውን ትሕትናቸውንና ደግነታቸውን በማድነቅ አስፋፍተው ጽፈ ውት ይገኛል ። እነዚህ የኢትዮጵያ መናንያን ከምስተኛ መቶ ዓመተ ምሕረት ጀምረው ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ሥራ በሠራባቸው በቅዱሳት መከናት ገዳማት አቅንተው ማኅበር ሠርተው ከግሪክ ኦርቶዶክስ ማኅበር በተቀር ሌላ ክርስቲያን ሳይቀድማቸው በቅዱሳት መከናት ባለርስት ባለመብት ሆነው በቀደምትነት የሚኖሩ መሆናቸውን ለመ ረዳት መጽሐፉን መመልከት ነው ። እነዚህ መናንያን መነከሳት በኢየሩሳሌም ይህን የመ ሰሉ ገዳማት አቅንተው በመከናት ቅዱሳት የሃይማኖት አገልግሎታቸውን እየፈጸሙ የኖሩት እንደነ አጼ ዘርአ ያዕቆብ ያሉ ደጋግ ነገሥታትና ፣ አንዳንድ ምእመናን ለነፍሳ ቸው ሲሉ በምጽዋት ከሚቸርዋቸው እርዳታ በተቀር በራሳቸው ገድልና ትሩፋት ሥራ ጽረው ግረው ከሚያገኙት የዕለት ምግብና ከዓመት ልብስ በቀር እንደ ዛሬ ዘመን ሁሉ ለገዳሙ መረጃ የሚሆን ርስት ጉልት አልነበራቸውም ። ለምሳሌ ስለ አጼ ዘርአ ያዕቆብ ከተጻፈው ታሪክ ውስጥ እንዲህ የሚል ይገኛል ።

በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ አሐዱ አምላክ ፣ በኵሉ ልብየ ዘኪያሁ አመ ልክ፥ በኵሉ ኀይልየ ወበኵሉ ነፍስየ ወበኵሉ ሕሊናየ ዘበቱ አሰምክ፥ ዘእትኑዝ በሐብለ አምልኮቱ ዘኢይትበተክ ዘበቱ አሐዩ ለዝሉፉ ወኢይትሀወክ ። ተጽሕፈት ዛቲ መል እክት ውስተ ዛቲ መጽሐፈ ሲኖዶስ እምኀቤየ እምኀበ ዘርአ ያዕቆብ ዘስመ መንግሥ ትየ ቈስጠንጢኖስ እምአመ አንበረኒ አምላክ እስራኤል በብዝኀ ምሕረቱ ዲበ መንበረ መንግሥተ ኢትዮጵያ በ፳ ዓመት እንዘ ሀሎኩ ውስተ ሀገረ ሽዋ እንተ ትሰመይ ተጕ ለት ፣ ትብጻሕ ኀበ ፍቁራንየ ማኅበረ ቅዱሳን እለ ይነብሩ ውስተ ኢየሩሳሌም ሀገር ቅድ ስት በሰላመ እግዚአብሔር አሜን ።

አስተበፅዓክሙ ፈድፋደ ፣ ቀዳሚ ከንክሙ ፂዉዋነ ለቃለ ወንጌል ዘይቤ ዘኢኀደገ አባሁ ወእሞ ወብእሲቶ ወውሉዶ ወገራውሂሁ ወኵሎ ዘቦ፥ ወበእንተዝ ኀደግሙ ዓለመ ወቦእክሙ ውስተ አርዑተ ምንኵስና፥ ወዳግመ ፄወወክሙ ቃለ ነቢይ ዘይቤ ኢይበውእ ውስተ ጽላሎተ ቤትየ ወኢየዓርግ ውስተ ዓራተ ምስካብየ ፣ ወኢይሁበን ንዋመ ለአዕይ

ንትየ ወኢ.ድቃሰ ለቀራንብትየ ፡ እስከ እረክብ መከኖ ለእግዚአብሔር ፡ ወማኅደሮ ለአ ምላከ ያዕቆብ ።

ወበእንተዝ አዋበዕክሙ ለነጊደ ኢየሩሳሌም ሀገሩ ለንጉሥ ዐቢይ ፡ እንዘ ኢትፈርሁ ምንዳቤ ፍኖት ሐሩረ መዓልት ወቍረ ሌሊት ወቀትለ ፈያት ። ወሶበ በጻሕክሙ ህየ ተፈጸመ ላዕሌክሙ ዘተብህለ በነቢይ "ንበውእ እንከሰ ውስተ አብያቲሁ ለእግዚአብሔር ወንሰግድ ውስተ መከን ኀበ ቆመ እግረ እግዚእነ„ ፡ ወከፈለክሙ ከመ ተአምኁ መከናቲሁ ቅዱሳተ እመከነ ቍጽረቱ እስከ መከነ ዕርገቱ ፡ ወበእንተዝ እነሂ እትአመን በጸሎትክሙ ወበኵሉ ምንዳቤክሙ በእንተ ፍቅረ እምላክ ዘበጽሐክሙ እምሥርወ ልብየ ፡ እኤምኀክሙ እንዘ እብል ሰላም ለክሙ ደቂቀ ኢትዮጵያ ዘኄወወተክሙ ኢየሩሳሌም ምድራዊት ከመ ታብጽሕክሙ ኀበ ኢየሩሳሌም ሰማያዊት ፡ ሰላም ለሃይማኖትክሙ እንተ በሥላሴ ፍጽምት ወለምንኵስናክሙ እምሳለ መላእክት ።

ሰላም ለአእጋሪክሙ እለ ኬዱ ፡ ወለአእዳዊክሙ እለ ጐድጐዱ ፡ ወለከናፍሪክሙ እለ ሰዐማ በከመ ፈቀዱ፡ ወለአዕይንቲክሙ ነጽር እለ አግሃዱ ፡ ገሊላሃ ኀበ ተሰብአ ወቤተልሔምሃ ኀበ ተወልደ እምላክነ ንጉሠ ዘዚአነ ጠባይዐ ፡ ወንለሃ ኀበ ሰከበ ወተፀንግዐ ፡ ናዝሬትሃ ኀበ ተሐፅነ ወዮርዳኖስሃ ኀበ ተጠምቀ ከመ ያንጽሐነ ፡ ቆሮንቶስሃ ኀበ ጾመ በእንቲአነ ፡ ቀራንዮሃ ኀበ ተሰቅለ ከመ ይቤዝወነ ፡ ወጎልጎታሃ ኀበ ተቀብረ ወተንሥአ ከመ ያሕይወነ፡ ደብረ ዘይትሃ ኀበ ዓርገ እምህየ ኀበ አቡሁ እምላክነ ከመ ያብአነ ውስተ ውሳጤ መንጦላዕት አርያማዊ ኀበ ቦአ ለሊሁ ሐዋርያነ ዘእምቅድሜነ ፡ ጽርሐ ጽዮን ኀበ ወረደ ጰራቅሊጦስ ኀበ ሐዋርያት አበዊነ ።

ወሰላም ካዕበ ለአዕይንቲክሙ እለ ነጸራ ብርሃነ፡ ዘይወፅእ እመቃብሪሁ ለእግዚእነ በቀዳሚት ሰንበት ዘውእቱ መኀትወ ፋሲካነ ። ሰላምክሙ ወፍቅርክሙ ጸሎትክሙ ወበረከትክሙ የሀሉ ምስሌየ ለዓለመ ዓለም አሜን ።

ናሁ ፈኖኩ ለክሙ ዘንተ መጽሐፈ ሲኖዶስ ከመ ትትናዘዙ በቲ በቀዳሚት ሰንበት ወበእሑድ ከመ ይኩንኒ ተዝካረ በኀቤክሙ ለዓለመ ዓለም አሜን ።

ይእዜኒ ሠራዕኩ ለክሙ አነ ዘርአ ያዕቆብ ዘስመ መንግሥትየ ቈስጠንጢኖስ እምአመ አንበረኒ እግዚአብሔር ዲበ መንበረ መንግሥት እምአመ ንግሥየ በ፳ ዓመት እምድረ ዝበላ ወእመንፈቁ ዘይወፅእ ግብሩ በ፱ ዓመት ፪ ሐልቀ ወርቅ ከመ ይኩኖሙ ሲሳዮሙ ወዓራዘሙ ለማኅበረ ኢየሩሳሌም ወሀብኩ ከመ ይኩን ተዝካርየ ወለተዝካረ እግዝእትየ ማርያም ። ወግብሩ በዓላ ለብሕቲትየ አመ ፩ ለግንቦት ልደታ ወአመ ፳ወ፩ ለጥር ዕረፍታ ። አመ ፲ወ፮ ለነሐሴ ፍልሰታ ፡ ወበዓለ ወልዳሂ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ አመ ፳ወ፱ ለታኅሣሥ በዘተወልደ ፡ ወግበሩ በቤተልሔም በዓለ ፋሲካ ዝውእቱ ትንሣኤ ሞቱ ማሕየዊት ፡ ወካዕበ አክብሩ ኵሎ በዓላቲሃ ለእግዝእትነ ማርያም ዘሀሎ ውስተ መጽሐፈ ተአምሪሃ ፴ወ፱ ወዓዲ ከመ ታኅትዉ ሊተ ቀናዲለ ውስተ መቃብረ እግዚእነ ፩ ፡ ወበውስተ እንቀጸ ዴዴሁ ፩፡ በየማኑ ፩ ፡ ወበፀጋሙ ፩ ፡ ወኀበ ግንዘቱ ፫ ፡

ወበኀበሂ ርእየቶ መግደላዊት ፩፣ ኀበ ሀይከል ዘዚእነ ፫፣ ወክዕበ ኀበ ዝኀሬ ለእግዝ እትነ ማርያም በጌቴሴማን ፫፣ ኀበ ተወልደሂ እግዚእነ በቤተልሔም ፩፣ ወኀበ ዓርገ እግዚእነ ውስተ ደብረ ዘይት ፩፣ ከመዝ አኀትዉ በንዋየ ዚአየ ወትረ ወኢ.ታብጥሉ ወኢ.ትደምሩ ንዋየ ባልእ፣ እስመ አነ እንግዝ በሐብለ ፍቅርከሙ፣ ጸሎትከሙ ወበረ ከትክሙ የሀሉ ምስሌየ ለዓለመ ዓለም አሜን ።

አፍቁሬንየ ኢ.ትበሉ ለባሕቲትነ ይወርድ ብርሃን ከመ ኢ.ይኩን ተመክሖ ላዕሌከሙ እስመ አንትሙ ተአምሩ ከመ ተመክሖ ያመጽእ እኩያተ ወትሕትና ያመጽእ ሠናያተ፣ ሰላም ለከሙ ወሰላመ እግዚአብሔር የሀሉ ምስሌከሙ አሜን ።

ትርጓሜ ው ፤ በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ፩ አምላክ፣ በፍጹም ልቡና ዬ እሱን የማመልከው፣ በፍጹም ኃይሌ፣ በፍጹም ነፍሴና በፍጹም ሕሊናዬ እምጠጋ በት በማይበጠስ እምልከቱ ገመድ የተያዝሁ ለዘለዓለሙ እሱን በማመን ሳልታወክ በምኖርበት ባንድ አምላክ ስም እምኜ ይህችን ደብዳቤ እጽፍላችሁ አለሁ ።

ይህች ደብዳቤ ስመ መንግሥቴ ቴስጠንጢኖስ በሆነ በኔ በዘርአ ያዕቆብ እጅ ተጻ ፈች ። የእስራኤል አምላክ በቸርነቱ ብዛት በኢ.ትዮጵያ መንግሥት ዙፋን በስቀመጠኝ በ፳ኛው ዓመት በሸዋ አውራጃ ውስጥ ተዮለት በምትባል (ወረዳ) ሳለሁ የተጻፈች ደብዳቤየ በእግዚአብሔር አንድነት፣ በቅድስት አገር በኢ.የሩሳሌም ለሚኖሩ ወዳጆ ቹና ቅዱሳን ማኅበር ትድረስ ። አሜን (በእውነት) ።

መጀመሪያ ነገር፣ እናት አባቱን፣ ሚስቱንና ልጆቹን፣ እርሻውንና ያለውን ሁሉ ያል ተወ ለሚለው ለወንጌል ቃል ምርኮኞች ሆናችኋልና እጅግ አመሰግናችኋለሁ ። ስለ ዚህም ዓለምን ትታችሁ በምንኵስና ቀንበር ውስጥ ተጠምዳችኋልና፣ዳግመኛም የእግ ዚአብሔር በታውን፣የያዕቆብ አምላክ ማደሪያውን እስከገኝ ድረስ ወደቤቴ ጥላ ውስጥ አልገባም ። ወደምኝታዬ አልጋ ላይም አልወጣም፣ለዓይናቼም እንቅልፍን፣ለቅንድ ቦቼም ሽልብታን አልሰጣቸውም ያለው የነቢዩ ቃል ማርኳችኋልና ስለዚህ የደገኛው ንጉሥ አገር ወደምትሆን ወደ ኢ.የሩሳሌም ለመሄድ ቈረጣችሁ ።

በመንገዱ የሚገኘውን ልዩ ልዩ መከራንና የቀን ሐሩር የሌት ቍርን የወንበዴዎ ችን አደጋ ሳትፈሩ ለመሄድ ቈረጣችሁ ።

ከዚያም በደረሳችሁ ጊዜ “እንግዲህ ወደ ቤቶቹ እንገባለን፣የጌታችንም እግር ከቆመበት እንሰግዳለን„ ተብሎ በነቢዩ የተነገረው ቃል ፣ ለናንተ ተፈጸመላችሁ ።

ከተፀነሰበት ጀምሮ እስከ ዓረገበት ድረስ ያረፈባቸውን ቅዱሳት በታዎች እጅ ትነ ሡ ዘንድ አደላችሁ ። ስለዚህ እኔም ስለ አምላክ ፍቅር በደረሰባችሁ ጾዋትወ መከራና በጸሎታችሁ በፍጹም ልቡናዬ እታማመናለሁ ።

ምድራዊዋ ኢ.የሩሳሌም ወደ ሰማያዊዋ ኢ.የሩሳሌም ታደርሳችሁ ዘንድ የማረከቻ ችሁ የኢ.ትዮጵያ ልጆች ሆይ፣ ለናንተ ሰላምታ ይገባል እያልኩ እጅ እነሣችኋለሁ ።

ፍጽምት በምትሆን ሥስትነት ለምታምን ሃይማኖታችሁም ሰላምታ ይገባል ። የመ ላእክት አምሳል ለምትሆን ምንኵስናችሁም ሰላምታ ይገባል ። ኢ.የሩሳሌም ለመሄድ

ለደከሙ እግሮቻችሁና ደጅ ለጸፉ እጆቻችሁ፣ እንደ ፍላጎታቸው ቤተ መቅደስን ለሳሙ ከንፈሮቻችሁ ሰላምታ ይገባቸዋል ።

ሰው የሆነበት ገሊላን፣ አምላክ የኛን ባህርይ ባሕርይ አድርጎ የተወለደበት ቤተ ልሔምንና የተጠጋበትና የተኛበት በረትን፣ያደገበት ናዝሬትን፣እኛን ከኃጢአት ያነጻን ዘንድ የተጠመቀበት ዮርዳኖስንና ስለኛ የጾመበት ገዳመ ቆሮንቶስን፣ እኛን ለመታደግ የተሰቀለበት ቀራንዮንና እኛን ያነሣን ዘንድ ተቀብሮ የተነሣበት ጎልጎታን፣ ሐዋርያችን እርሱ፣አስቀድሞ ወደ ገባበት አርያማዊ (ሉዓላዊ) ወደ ሚሆን ውሳጤ መንጠላዕት እኛን ያገባን ዘንድ ወደ አባቱ ያረገበት ደብረ ዘይትንና፣ መንፈስ ቅዱስ ወደ አባቶቻችን ሐዋርያት የወረደበት ጽርሐ ጽዮንን፣ በግልጥ ለማየት ለበቁ ዓይኖቻችሁ ሰላምታ ይገባቸዋል ።

ደግሞም የፋሲካችን ዋዜማ በሆነችው በፊተኛይቱ ሰንበት፣ ከጌታችን መቃብር ውስጥ የሚወጣውን ብርሃን ላዩ ዓይኖቻችሁ ሰላምታ ይገባል ። ሰላምታችሁና ፍቅራ ችሁ፣ ጸሎታችሁና በረከታችሁ ለዘለዓለሙ ከኔ ጋር ይኑር (በኔ ላይ ይደር) አሜን (በእውነት) ።

ይኸውና፣በመጀመሪያይቱ ሰንበትና (ቅዳሜ) በአንደኛይቱ ሰንበት ትጽናኑበትና በና ንተ ዘንድ ለዘለዓለም መታሰቢያ ይሆነኝ ዘንድ ይህን ደብዳቤ ጽፌ ላክሁላችሁ ።

አሁንም ስመ መንግሥቴ ቈስጠንጢኖስ የሆነ እኔ ዘርአ ያዕቆብ እግዚአብሔር በመ ንግሥቱ ዙፋን ባስቀመጠኝ በ፰ኛው ዓመት የሚከተለውን ሠራሁላችሁ ።

ከዝበላ ወረዳ የሚወጣውን ግብር እኩሌታውን በሁለት በሁለት ዓመት አንዳንድ መቶ (ሕልቀ ወርቅ) የወርቅ ወጭት ምግባቸውንና ልብሳቸውን ይሆን ዘንድ በኢየሩ ሳሌም ለሚገኙት ማኅበር ሠርቸላቸዋለሁ ።

ለኔ መታሰቢያ በእመቤታችንና በኔ መካከል መታሰቢያ ሆኖ ይኖር ዘንድ፣ የል ደታ በዓል በሚከበርበት ግንቦት ፩ ቀን፣ያረፈችበት ጥር ፳፩ ቀን፣በዓለ ፍልሰታ የሚ ከበርበት ነሐሴ ፲፮ ቀንና ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የተወለደበት በሚውልበት ታኅ ሣሥ ፳፱ ቀን በቤተ ልሔም አድርጉ ።

እንዲሁም ማሕየዊ ከሚሆን ከሞቱ የተነሣበትን የፋሲካን በዓል አክብሩ ። ዳግመ ኛም፣ በተአምሯ መጽሐፍ ውስጥ የሚገኙትን ፴፫ የእመቤታችንን በዓላቶች አክብሩ።

ደግሞም፣ ጌታችን በተቀበረበት መቃብር ላይ አንድ መብራት፣ በቀኙና በግራው በሚገኙ ደጃፎች አንዳንድ መብራቶች፣ ከተገነዘበቱ ላይ አንድ፣ ማርያም መግደላዊት ጌታችን ካየችበት ቦታ ላይ አንድ፣ በኛው ሃይከል ላይ ሦስት፣ እመቤታችን በተቀበረ ችበት በጌቴሴማን ሦስት፣ ጌታችን በተወለደበት በቤተ ልሔም አንድ፣ ጌታችን ካረገ በት ደብረ ዘይት ላይ አንዳንድ መብራቶች ዘወትር በኔው ገንዘብ አብሩባቸው፣ አታስታ ጕሉ ። የሌላን ገንዘብ ወይም መብራት አትጨምሩ ። እኔ በገመድ ፍቅራችሁ የተያዝኩ ነኝና፣ ጸሎታችሁ፣ ልመናችሁና በረከታችሁ ለዘለዓለሙ በኔ ይደር፣ አሜን (በእውነት)።

ወዳጆቼ ሆይ! መመከት እንዳይሆንበችሁ ለኛ ብቻ ነው ብርሃን የሚወርድልን አትበሉ። ትምክህት፥ ክፉ ነገርን እንደሚያስከትል፥ ትሕትና ግን በጎ ነገርን እንደ ሚያመጣ እናንተ ታውቃላችሁና።

ሰላም ለናንተ ይሁን፥ የእግዚአብሔር ፍቅርና አንድነት ከናንተ ጋራ ይኑር። አሚን፥ (በእውነት)።

እንደዚሁም፥ እንደ ኢ. ቀ. በ፲፩፻፲፯ ዓ. ም. ከኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና ሕዝበ ክርስ ቲያን ገንዘብ መጥቶላቸው በቅዱሳት መከናት የነበራቸውን መቅደሶችና ገዳማት እንዳሳ ደሱ በ፫ኛው ማስረጃ ተጽፎ ይገኛል። እንደ ታሪክ ነገሥቱ፥ ዘመኑ በአጼ ልብነ ድንግል ጊዜ ነው። እነዚህ ማኅበረ መነከሳት እንደዚሁ ከኢትዮጵያ ነገሥታትና ምእመናን በሚ ደርሳቸው ምጽዋት እየተደገፉ ሲኖሩ ከግራኝ ጦርነት ወዲህ የቱርክ መንግሥት እንደ ጠላት አይቶ ችላ ስላላቸው ከኢትዮጵያም እርዳታ ስላቋረጠባቸው በድካም ላይ ሳሉ በኢትዮጵያችን ዘመነ መሳፍንት በሚባለው ዘመን ከአስራ ሰባተኛው መቶ ዘመን ወደ ዚህ ደግሞ የባሰውን ፍጹም ድህነት ደርሶባቸው በቅዱስ መቃብር (በጎልጎታ) ውስጥ የነበራቸውን የርስት መብት ለአርመኖች ለቀው ዴር ሥልጣን ከሚባለው ከጎልጎታ ቤተ ክርስቲያን ጋር በምሥራቃዊ ክፍል በኩል ገጥሞ ከሚገኘው ገዳማቸው ብቻ ተወስነው ሠፈሩ። ከዚህ በኋላ በጎልጎታ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ያሚገኘው የኢትዮ ጵያ ንብረት ሁሉ ለአርመኖች ተለቆ ስለ ነበር የግሪክ ፓትርያርክ የኢትዮጵያ ንብረት ከአርመን እጅ መውደቅ አይገባውም ሲል፥ ተቃውሞ በሁለቱ ማኅበሮች በግሪክና በአ ርመን መክከል በኢትዮጵያ ንብረት ምክንያትና በየጊዜው የተፈጠረው ትግል ልክ የለውም።

ቀጥሎም አብዛኛውን ንብረታቸውን ለቀው በዴር ሥልጣን ገዳም ውስጥ ሲኖሩ በአሥራ ሰባተኛ መቶ ዘመን ማለቂያ (፲፯፻፹) ዓ. ም. ግድም መዓልም አብራሂም (ኢብራሂም ዡሕሪ) የሚባል ግብጻዊ ሰው ስምንት አገልጋይ (ባሮች) ይዞ ዴር ሥል ጣን ገዳም ደርሶ ወደ መነኮሳቱ መጥቶ አባቶቼ የሃይማኖት ወንድማችሁ ነኝ በከተማው ቤት ስለ አጣሁ አባክችሁን ከእናንተ ቦታ ማረፊያ ስጡኝ አላቸውና መነኮሳቱም አጽ ፋቸውን ለብሰው ጸሎት ከማድረግ በተቀር የሰውን ተንኰል የማያውቁ ደጋግ መነኮ ሳት ነበሩና ፈቅደውለት ከገዳማቸው ገባ። መዓልም አብራሂም ዡሕሪም የተማረ ሰው ነበረና በኢየሩሳሌም ከቱርክ መንግሥት ሥራ አግኝቶ ከፍ ያለ ባለ ሥልጣን ሆነ። በመነኮሳቱም ላይ ሠለጠነና ለነሱ ተጠያቂ ነኝ እስከ ማለት ደርሶ ከቤታቸው ከፍሎ ይስ ሐቅ ቤይ ለሚባል ሰው በኪራይ ሸጦ ወዲያውም አንድ ካህን ስደዱልኝ ብሎ ወደ ግብጽ ልኮ ቀሲስ ጊዮርጊስ የሚባለውን ሕጋዊ ቄስ ላኩለትና በገዳሙ አስገባው። አብራሂም ዡሕሪ ሲያልፍም፥ ቀሲስ ጊዮርጊስ በሱ ሥፍራ ለገዳሙ ዋና እኔ ነኝ ብሎ ተተከና እን ዲያውም ከዴር ሥልጣን ገዳም ቦታ ከፍሎ ምሥራቁን ክፍል ለመስከቦች ሸጠ፥ መነ ከሳቱ ግን ይህ ሁሉ ሲሆን ጥቃታቸውን የሚገልጹበት ቋንቋ ባለማወቃቸው የመጣ ግብ

ጳዊ የኛ ጥገኞች ናቸው እያሉ ያንገላቷቸው ጀመር ። ከዚህ የባሰውን ደግሞ ፲፰፻፳ ዓ. ም. ቤቱን እናሳድሰዋለንና ልቀቁ ብሎ ከንዋዛቸው ከመኖሪያ ቤታቸው አስወጣቻ ውና ከታደሰም በኋላ ተመልሰው እንዳይገቡ አድርገዋቸው ዛሬ የኛ መነኮሳት ከሚገኙት ዋና ሥፍራ ውስጥ ብቻ ተወስነው ቀሩና ዋናውን የኢትዮጵያ ገዳም ግን ግብጾች በተንኰል ገብተው እስከሁንም ይዘዉታል ። የኛ መነኮሳት ግን ሥፍራቸውን ለቀው መውደቂያ ቢያጡ በዚሁ ባሉበት ቦታ ያሸከከ ዋሻ የመሰሰለ የጭቃ ጐጆ እያበጁ መቀመጥ ግድ ሆነባቸው ። እንዲሁም ሆነው በመከራና በሥቃይ ሥፍራ ሲኖሩም ፲፰፻፴፰ ዓ. ም. የወረርሽን ( ተስቦ ) በሺታ ገብቶ የኢትዮጵያን መነኮሳት አንድ ሳይቀር በሽታው ጨረሳቸውና አሁንም ግብጾች ጊዜው ረድቷቸው የገዳሙን መክፈቻ ፈጽመው እጅ አደረጉና በተላላፊ በሽታ አመከኙተው በኢትዮጵያውያን ቤተ መዛግብት (ዕቃ ቤት) ውስጥ የነበረውን የርስት ማስረጃ ኩሻንና (ከርታ) ቅዱሳት መጻሕፍት የመላበትን ግምጃ ቤት በሙሉ በእሳት አቃጠሉት ። በዚህ ጊዜ የኢየሩሳሌም ገዥ ኢብራሂም ፓሻ የምሥር ሰው በመሆኑም ደህና አጋጣሚ አገኙና የፈቃደቸውን ለመሥራት ተመቻቸው። ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ነው ከፕቶች ደሬር ሥልጣን የሚባለው ገዳም የከፕቶች ርስት ነው እንጂ የሐበሾች አይደለም ማለትን ደፍረው ለመናገር የቻሉት ። ይህንንም ቃጠሎውን ለመረዳት የእንግሊዝ ቆንሲል ፊንና ቢሾፕ ጐባት ከመንግሥታቸው ጋር የተጻጻፉትን ዜና ኢትዮጵያ በሀገር ቅድስት ኢየሩሳሌም ከሚባለው ፩ኛ መጽሐፍ ውስጥ መመልከት ይጠቅማል ፣ ከዚህም በተቀር በኢየሩሳሌም በኢትዮጵያ ገዳም ያለውን ታሪክ ተመልከት፣ በዚህ ጊዜ ራስ ዓሊና ደጃዝማች ውቤ ቀጥሎም አጼ ቴዎድሮስ ለእንግሊዝ ንግሥትና ለእስክንድርያም ፓትርያርክ ተጻጽፈው ነበር ። ይሁን እንጂ የተፈጸመ ነገር የለም ።

## አ ፄ ዮ ሐ ን ስ

አጼ ዮሐንስ በነገሡ ጊዜ ይህን የዜጎቻቸውን ጥቃት ለማስወገድ ብዙ ሥራ ሠርተዋል ከሥራቸውም አንዱ የኢትዮጵያ መነኮሳት መጠጊያ ሥፍራና መድረሻ አጥተው የአርመን ገዳም ጥግ አድርገው ለዕለት ራት እየተገዙ ወራዳ ኑሮ መኖራቸውን ሰምተው ከአርመን ጥገኝነት ተለዩ እንጂ ለናንተ መሆን አያቅተኝም ብለው የጻፉት ደብደቤ እንደሚያስረዳው በየጊዜው ለማኅበሩ ቀለብ ይልኩት የነበረው ገንዘብ ልክ የለውም ። ይህም ብቻ ሳይሆን ሰፊ መሬት ገዝተው ደብረ ገነት ኪዳነ ምሕረት ቤተ ክርስቲያንና ቤተ መነኮሳትም የውሀ ጉድጓድም (ቢር) አሠርተው ማኅበሩ በነፃነት የሚኖሩበት ገዳም ሠርተዋል፤ ደግሞም ጉራዕ ላይ ባደረጉት በቱርኮች ጦርነት ከምርኮ የተገኘውን ፮ ሣጥን ሙሉ ወርቅ በኢየሩሳሌም ለሚኖሩ ማኅበር መረጃ ይሁን ብለው ልከዋል ። የሳጥኑም ምልክት እስከሁን ይገኛል ።

## አፄ ምኒልክ ።

አፄ ምኒልክም በነገሡ ጊዜም በኢየሩሳሌም የሚኖሩት ዜጎቻቸው ማኅበረ መነኮሳት የዴር ሡልጣን ገዳም መክፈቻ በግብጾች እጅ ከተያዘ በኋላ፥ በውስጡ የሚኖሩትን መነኮሳት በሩን ቈልፈው መግቢያና መውጫ እያሳጡ ቤተ ክርስቲያናቸውንም ዘግተው የሃይማኖት አገልግሎት እንዳይፈጽሙ በማድረግ የሚፈጽሙባቸውን ስቃይና የሚሠሩባቸውን ግፍ በሰሙ ጊዜ በ፲፱፻፩ ዓ.ም. ደጃዝማች መሸሻ ወርቄን ልከው ከቱርክ ሡልጣን ዓብደልሐሚድ ጋር በመላላክ የዴር ሡልጣን ገዳምን ቍልፍ ለማስመለስ ብዙ ሠርተው ነበር ። ነገር ግን ፥ ግብጾች በተንኰል ከኢየሩሳሌም ገዥ ጋር ተመሳጥረው ከሡልጣኑ የተላለፈውን ትእዛዝ ከተግባር እንዳይውል ቢያደርጉባቸውም ደጃዝማች መሸሻ በርትተው የኢትዮጵያ መነኮሳት በነፃ የሚጠቀሙበትን ከዴር ሡልጣን በምሥራቅ በኩል አዲስ በር አስከፍተዋል ።

ስለ ዴር ሡልጣን ገዳምና ግብጾች ስለ ዘጉዋቸውም አርባዕቱ እንስሳንና ቅዱስ ሚካኤልን ሁለቱን ቤተ ክርስቲያኖች ርስት ጕዳይም ፥ በኢየሩሳሌም ከሚገኙት የሃይማኖት ባለሥልጣኖችና ከነዋሪ ሕዝበ ክርስቲያኖችም በምስክርነት ቃል ጠይቀው የሰበሰቡዋቸውን ጠቃሚ ማስረጃዎች ከኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ጽሕፈት ሚኒስቴር ሐርሽቭ ተገኝተው ይኸውና ለዛሬው ክርክራችን ዋና ጠቃሚ ሆነው በዚሁ መጽሐፍ ውስጥ ከ፩ እስከ ፲፩ኛ ቍጥር ክልሼ የተጻፉት ማስረጃዎች ናቸው ።

አፄ ምኒልክ ከዚህም ይበልጥ የደብረ ገነት ኪዳነ ምሕረት ቤተ ክርስቲያንን በዓፄ ዮሐንስ ሞት የተቋረጠውን ሥራ አስፈጽመዋል። ለማኅበሩ መረጃ መተዳደሪያ የሚሆን (200.000) ሁለት መቶ ሺ ማርያ ትሬዛ ብር ባንክ አግብተው የሚከራይ ቤት ሠርተው ማኅበሩ ራሳቸውን ችለው በደምብ እንዲተዳደሩ አድርገዋል ።

እቴጌ ጣይቱም በተለይ መሬት ገዝተው ከፍ ያለ ኪራይ የሚከራዩ ቤቶች አሠርተው እጅግ ጠቃሚ የሆነ እርዳታ አድርገዋል ።

ከዚህም ሌላ በየጊዜአቸው ፥ ለኢየሩሳሌም ማኅበር መረጃ ርስትና ቤት የሰጡ የሚከተሉት ናቸው ። ክቡር ራስ ወልዴ ፣ ክቡር አፈ ንጉሥ ነሲቡ ፣ ክቡር ደጃዝማች ባልቻ ፥ ክብርት ወይዘሮ ደስታ ፥ እነዚህ ጌቶች ሁሉም ቦታ ገዝተው ቤት ሠርተው በመስጠት ለገዳሙ ታላቅ እርዳታ አድርገዋል ።

## አፄ ኃይለ ሥላሴ ።

ግርማዊ ቀዳማዊ አፄ ኃይለ ሥላሴ ን.ነ. ዘኢትዮጵያ፥ ገና የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥት አልጋ ወራሽና ባለሙሉ ሥልጣን ሲባሉ በ፲፱፻፲፮ ዓ-ም ኢትዮጵያን ከተባበሩት የዓለም መንግሥታት ማኅበር በገቡበት ዘመን ኢየሩሳሌም መጥተው ለኢትዮጵያ ገዳም አንድ ዘውድ አበርክተው ተመልሰዋል። ከዚህም ሌላ ኢየሩሳሌም በአይሁድና በዓረቦች መካከል በ፲፱፻፵፪ ዓ-ም፥ በተነሣው ጦርነት ምክንያት በኢየሩሳሌም የሚገ

ኙት የኢትዮጵያ ገዳማት ንብረታቸው ሁሉም ተበላሽቶ ችግር ስለ ደረሰባቸው ገዳማቱ እንዳይጠፉ አስበው ከኢትዮጵያ መረጃ ገንዘብ እንዲሰጣቸው አዝዘው ይኸውና በመ ት በመቱ ከኢትዮጵያ ን. ነገሥት መንግሥት የገንዘብ ሚኒስቴር ብዙ ገንዘብ እየተላከ ላቸው ማኅበሩ እንዲረዱ አድርገዋል ። ከዚህም ሌላ ደግሞ ጥንት የክርስቲያን መቃ ብር ቦታ የነበረው በጦርነት ተይዞ ገዳማቱ የሚቀብሩበት ሥፍራ ቢያጡ አልአዛር ከሞት ከተነሣበት ከተማ ዳር ፲፱ ሺሕ ካሬሜትር መሬት አስገዝተው በኢየሩሳሌም የሚ ኖረው ሕዝባቸው እንዲቀበርበት ፈቅደው በብዙ ሺሕ ብር ቅጥሩን አስቀጥረው ሰጥተዋ ል ፣ ወደፊትም ረጅም ዕድሜ ይስጣቸው እንጂ በግርማዊነታቸው ያለን ተስፋ ብዙ ነው ።

## እ ቴ ጌ   መ ነ ን ።

ግርማዊት እቴጌ መነን እኒህ ብፅዕት ንግሥት ለኢየሩሳሌም ያደረጉት እርዳታ እ ጅግ ብዙ ነው ።

አንደኛ በ፲፱፻፲፫ ዓ-ም ልዕልት ወይዘሮ መነን ሲባሉ ኢየሩሳሌም መጥተው ለማኅበሩ ብዙ የልብስና የገንዘብ እርዳታ አድርገው አንድ ባለፈርጥ የከበረ የዕንቍ አክ ሊልና ንዋየ ቅድሳት ለኢትዮጵያ ገዳም ሰጥተው ተመለሱ ።

ሁለተኛ ደግሞ ፣ በዮርዳኖስ የሚኖሩት የኢትዮጵያ መነኮሳት መኖሪያ ቤትና ቤተ ክርስቲያን ሳይኖራቸው በየጫካው ውስጥ የሳር ጐጆ ቀልሰው በንዳድ በሽታ እየተሰ ቃዩ ሲኖሩ የነበሩትን ፣ ግርማዊት እቴጌ መነን ቤተ ክርስቲያንና ቤተ ማኅበሩን ባንድ ሕንፃ አያይዘው ታላቅ ገዳም አሠርተው ቤተ ክርስቲያኑን በቅዱስ ሥላሴ ስም በ፲፱፻፳፭ ዓ-ም አስባርከው ሰጥተዋል ። እነሆ ዛሬ በዮርዳኖስ ወንዝ ዳር ካሉት የክርስቲያን ማኅ በሮች የኢትዮጵያን ገዳም የመሰለ ዝግጅት ያለው ገዳም አይገኝም ። ከዚህም ሌላ ዛሬ ም ለዚሁ በዮርዳኖስ ወንዝ ዳር ላሠሩት ገዳም መረጃና ለሕንፃው መጠባበቂያ የሚ ሆን በኪራይ የሚረዳ ቤትም ባዲስ አበባ ከተማ ላይ በማሥራት ይገኛሉ ።

(ወይዘሮ አማረች ዋለሉ) እኒህ የተባረኩ ወይዘሮ አማረች ገና ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ በሕይወታቸው ሳሉ ጣዕመ ዓለምን ንቀው መንነው ወደ ኢየሩሳሌም መጥ ተው በተቻላቸው ሁሉ ችግረኛን እየረዱ እስከሁን ኢየሩሳሌም ተቀምጠው በሕይወት ይገኛሉ ። ለኢየሩሳሌም ገዳም ከኢያሪኮ ከተማ አታክልትና ቤት ያለበት ገነት የሆነ ፫ ሺህ ፱፻ ካሬ ሜትር ያህል ጥሩ ቦታ ገዝተው ለዮርዳኖስ ሥላሴ ቤተ ክርስቲ ያን መረጃ ይሁንልኝ ብለው ሰጥተዋል ።

## ማ ሳ ሰ ብ ።

ይህ ዓለም የሰው ዘር ሁሉ እየታየ የሚያልፍበት መተላለፊያ ጐዳና ነው እንጂ ማንም አይኖርበትና ጥቂት ዘመናት ቢኖርም ቀደም ተከተሉን የጥርጊያውን ተራ መረ ፋውን የመጠበቅ ያህል ቆይቶ በተራው ሁሉም መንገደኛ ስለሆነ እስኪያልፍ ድረስ እግረ መንገዱን እንደየዕድሉ እግዚአብሔር የከፈለውን ያህል ደግ ቢሆን ወይም ክፉ

የተቻለውን ሠርቶ የጕዘው ተራ ሲደርስ እሱው ራሱ አላፊ ሃያጅ ነውና ባላፊው ጊዜ የማያልፍ ደግ ሥራን የሚሠራ ሰው ቅዱስ የመባል የክብር ስም ይወርሳል ።

ምስጋና ፣ በዚህ በሥራ መቅድም ላይ ቀደምት ሆነው ለተከታዮቻቸው የማኅበራዊ ኑሮ አብነት ሆነው ገዳማቱን ላቀኑልንና የሥራ መሪ ማስታወሻ ትተው ያለፉትንና ቋን ቋውን በማያውቁት በሀገር ቅድስት በኢየሩሳሌም ረኃቡንና ጽምኡን ታግሠው ለኢት ዮጵያ ትውልድ በቅዱሳት መካናት ይህን የመሰለ የሃይማኖትና የቅድስና መታሰቢያ ዝክረ ነገር የሆነውን ሥፍራ ትተውልን ያለፉት ብፁዓን አበው መነኮሳትን አስቀድሜ አመሰግናለሁ ።

እንደዚሁም ዛሬም በዘመናችን ይህን በቅዱስ ሥፍራ መብት ከክርስቲያን ማኅበ ሮች ጋር በተለየም ደግሞ በዴር ሡልጣን ገዳም ርስትነት ምክንያት ፣ በኢትዮጵያ ማኅ በርና በኮፕቶች መከከል ክዋንት ከአበው የተወረሰውን ታላቅ ጥቃት ከኢትዮጵያውያን ትከሻ ላይ አውርዶ ለመጣል የሐሳብ ተካፋይ ሆነው በብዙ ትጋትና በቅንነት ከኮፕቶች ጋር ያለውን ታላቅ ትግል ሲታገሉ የሚገኙትን የኢየሩሳሌምን ኑዋሪ ማኅበሮችና ከመንግ ሥት ባለሥልጣኖችም በኢየሩሳሌም የቆንስልነት ሥራ ይዘው ይህን አሁን አሳትመን የምናወጣውን ጽሑፍ በመፈለግ የረዱትን አቶ ሐዲስ ዓለማየሁን ፣ አቶ ሠረቀ ብርሃን ገብረ-እግዚእንና በሎንዶን የግርማዊ ንጉሠ ነገሥት አምባሳደር የነበሩት ክቡር አቶ አበበ ረታንም በኢየሩሳሌም ያልተገኙትን አሌክስ ዲባደን የጻፈውን ታሪክና የእንግ ሊዝ ባለ ሥልጣኖች በቅዱሱ ሥፍራ ስላለው የኢትዮጵያ መብት ብኢየሩሳሌም ከ፲፰፻፱ እስከ ፲፰፻፳፯ የሚለውን ማስረጃ ከለንደን ሚዜዩም በመፈለግ ስለረዱን፣ ሁሉንም ባሳ ዩት መልካም ፈቃድና በሠሩት አገልግሎት አመሰግናቸዋለሁ ።

በመጨረሻ ለመቅድም ንግግሬ ማሠርያ እግዚአብሔር ባይፈጥረን በዓለሙ ላይ በመ ኖር ፣ ግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መርጠው ባይልኩንም ሁላችንም ለሥራ ባልተገኘንም ነበርና በሰማያት ለእግዚአብሔር ፣ በምድርም መልካም ፈቃድ ላላቸው ለግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ምስጋና ይሁን ስል መቅድሙን አቆ ማለሁ ።

“ወዘንተ ኵሎ ገቢረክሙ በሉ አግብርት ድሩዓን ንሕነ፣ ወዘይደልወነ ለገቢር ገበርነ„ ሉቃ. ፲፯ ፥ ፲ ፥ እናንተ ደግሞ፣ እንደዚሁ የታዘዛችሁትን ሁሉ ሠርታችሁ ሥራ ፈት ባሮ ች ነን ልንሠራው የሚገባንን አድርገናል በሉ ።

አባ ፊልጶስ ።

# መ ግ ቢ ያ ።

ኢየሩሳሌም በእጁ እንድትወድቅ ከእግዚአብሔር ዘንድ ተፈቅዶለት ድል ካደረገ በኋላ ፣ የአማኞቹ መስፍን ተብሎ የሚጠራው ከሊፋ ዑመር ኢብን አልኸታብ አሚር አልማዕሙኒን ፣ በኢየሩሳሌም ለሚኖሩት ክርስቲያኖች በሰጠው ትልቁና ታሪካዊ ቃል ኪዳኑ (ዖማራይት ክቨናንት) ተጽፎ እንደተገለጸው ሁሉ ፣ የኢትዮጵያ ማኅበር ከጥንት ዘመናት ጀምሮ በቅዱስ መከን አካባቢ ውስጥ ሰፍሮ የቀረ መሆኑን እንገነዘባለን ።

ይኸ ቃል-ኪዳን ከሌላው ጽሑፍ ላይ በመጨመር "በኢየሩሳሌም ውስጥ የሚኖሩት ሌሎች ክርስቲያኖችም ማለት ጆርዳውያንና (ኩርዶች) ኢትዮጵያውያን (ሐበሾች) እንደዚሁም ቅዱስ መከንን ለመጐብኘት የሚመጡት ኤውሮጳውያን ፣ ከፕቶች ፣ አሶራውያን ፣ አርመኖች ፣ ኔስቶራውያን ፣ ያዕቆባውያንና ማሮኒታውያን . . . . . „ እያለ ይጠቅሳል ። ስለዚህ እስላሞች ኢየሩሳሌምን ድል ከማድረጋቸው በፊት ኢትዮጵያውያን (ሐበሾች) በሀገሩ ላይ በቀደምትነት የሚኖሩ እንጅ እንደሌሎቹ ሕዝቦች ለመጐብኘት ብቻ የሚመጡ ያለመሆናቸውን ቃል-ኪዳኑ በግልጽ ያስረዳል ያሳያልም ።

ኢትዮጵያ በመከን ቅዱስ ከሚገኙት ዋና ዋና አብያተ ክርስቲያናት ውስጥ በኢየሩሳሌም ከቅዱስ መቃብር (ጎልጎታ) ፣ በቤተልሔም ጌታ ከተወለደበት ቤተ ክርስቲያን ፣ ከቅድስት ድንግል ማርያም (ጌቴሴማኒ) ቤተ ክርስቲያንና ከሱልጣኑም ገዳም (ዴር ኤል ሱልጣን) ሌላ ፣ በተጨማሪ በቅዱስ መቃብር ዙሪያ ላይ አያሌ አብያተ ክርስቲያናትና መጸለያ ነዋሪ ቦታዎች ስለ ነበሩዋት የኢትዮጵያ ማኅበር በሀገሩ ላይ ርስት ይዞ ከኖረው ባለንብረት ሕዝብ አንዱ ክፍል ነበር ።

ከዚህም ሌላ የኢትዮጵያ ማኅበር ከቤኒ ዑስማን (የቱርክ ነገሥታት) ከሊፋዎች ስለ ነዋሪው ሕዝብ መብትና ይዞታ የታወጀውን መንግሥታዊ ድንጋጌዎች ፣ እንዲሁም ማስረጃ የሚሆኑ ሰነዶችና የሱልጣኑን ንጉሣዊ አዋጆች በእጅ ይዞ ቢገኝም ቅሉ ፣ አሁን በዚህ መግቢያ ውስጥ መግለጽ ባያሻኝም ፣ ከዘመን ብዛት የተነሣ ጭቅጭቅና ያልታሰበ ታሪካዊ መለዋወጥ ስለ ተፈጠረ ፣ ሰፊው የኢትዮጵያን ይዞታ መቀነስ ጀመረ ። ከሌሎቹ ወገኖች ይልቅ መንፈሳዊ እምነታችን የመነጨበት የኮፕት ቤተ ክርስቲያን በርስታችን ውስጥ ስለ ገባችብን በቅዱስ መከን የነበረው ይዞታችን በጣም እያነሰ ኼዷል ።

ባለፉት አያሌ ዓመታት ውስጥ ነገሩ እንዲመረመርልንና ዳኝነትም እንዲታይልን ለባለሥልጣኖቹ በማመልከት ፣ ጥንታዊ መብታችንና ይዞታችን እንዲመለስልን ጠይቀን ስለ ነበር ፣ ጳለስጢናን በሞግዚትነት ያስተዳድር የነበረው እንግሊዛዊ ሥልጣን

ጉዳዩን በዓለም መንግሥታት ማኅበር ትእዛዙ ለሚቋቋመው ኮሚሲዮን እንዲቀርብ ከወሰነ በኋላ ከሥልጣኑ ስለ ለቀቀ ፣ ጉዳዩ እፍጻሜ ሳይደርስ ቀርቷል ።

አሁን ግን የአገሩ አስተዳደር ወደ ሐሽሚታዊው የዓረብ መንግሥት አገዛዝ ዞሮ ስለሚገኝ ፣ የግርማዊው ሐሽሚት መንግሥት በነገሩ አስፈላጊውን ምርመራ በመፈጸም ጉዳትና በደል የደረሰበት ማኅበራችን ፣ ፍርድ እንዲያገኝ ያደርግልን ዘንድ ታላቅ ተስፋና እምነት ጥለንበታል ።

አሁን በእጃችን ከሚገኙት የመብታችን ማስረጃዎችና ሰነዶች ውስጥ በዚሁ መጽሐፍ በከፊል የምናሳትምበት ምክንያትና ሐሳብም ፣ ተመልካቹ ሕዝብና ባለሥልጣኖቹ እንዲያውቁት ሲሆን ፣ አስፈላጊ ሆኖ በተገኘ ጊዜም ጉዳዩን ለሚመለከት ባለሥልጣን ተጨማሪ ማስረጃዎች ለማቅረብ ዝግጁ ነን ።

ኢትዮጵያውያን በክብርና በሥነ ሥርዓት ተጠብቀን እንድንኖር ከመጀመሪያው የእስላም ሒጅራ (ስደት) በኋላ በደግነቱ ባዘዘልንና በደነገገልን በታላቁ የዓረቦች ነቢይ ቃል (ውል) መሠረት ፣ የጆርዳን መንግሥትና ሕዝቡም በግቡ እንዲሰማን በጥልቅ እየ ተማመንን እግዚአብሔርም ረዳታችን ሆኖ ሐሳባችንን እንዲባርክልን እንጸልያለን ።

በእግዚአብሔር ጸጋ ፣ በኢየሩሳሌም መንበር ፣
በሐሽሚታዊው የጆርዳን መንግሥትና በማእከላዊ ምሥራቅ ፣
ኢትዮጵያዊ ጳጳስ አባ ፊልጶስ ዘኢየሩሳሌም ።

## በመሐሪው እግዚአብሔር ስም

## አንደኛው ማስረጃ ።

### የዑመር ቃል-ኪዳን ።

### እግዚአብሔር በቸርነቱ እንዲጠብቀው ከምንሻ ከዑመር ኢብን አልኸታብ የተሰጠው አዋጅ ግልባጭ ።

እስላምነትን ለሰጠን ፡ በሃይማኖቱ ላከበረንና ነቢዩ መሐመድን በቸርነቱ ላስነሣልን ቀናውን መንገድ ላሳየን ፡ ከተበተንም በኋላ አንድ ላደረገን ለልባችን ኅብረትን ለሰጠንና በጠላቶቻችንም ላይ የድል አድራጊነትን ክብር በማግኘት የአህጉር ገዢነትን እንድንቀዳጅና ጥብቅ ተፋቃሪዎች እንድንሆን ላደረገን ለእግዚአብሔር ምስጋና ይግባው ፡ ሰላምና በረከቱም ለነቢዩ መሐመድ ይሁን ። እግዚአብሔርን የምታመልኩ ሁሉ ለዚህ አምላካዊ ጸጋ የሚገባውን ምስጋና ለእግዚአብሔር አቅርቡ ።

እኔ ዑመር ኢብን አልኸታብ መኖሪያው በኢየሩሳሌማዊት ደብረ ዘይት ለሆነው እጅግ ለተከበረውና ለታላቁ የመለከይት ሃይማኖት ፓትርያርክ ለብፁዕ ሰፍሮንዮስ ይኸንን መልእክቴን (ጽሑፌን) ቃል-ኪዳንና ሕጋዊ ውል አድርጌ በመስጠት እጽንቼለታለሁ ። ይህም ቃል-ኪዳን ለሕዝቦች ለካህናት ለመነኮሳትና እንዲሁም ለመነኮሳይያት በያሉበት ሰላምና ጸጥታ ያገኙበት ዘንድ ዘሚ የተባለው የጸጥታ አስከባሪነት ደንባችን በሚያዘው መሠረት ፡ የሕዝብ ደህንነትና ጸጥታ በእኛ በአማኞችና በተከታዮቻችን ሁሉ እንዲጠበቅ የሚያስገድዱ ስለ ሆኑ ፡ ሕዝቦች ታዛዢነትና ትሕትና እንደማሳየታቸው መጠን በሚቸግራቸው ሁሉ ፍርድ ያገኙበታል ። ለሕይወታቸው ለአብያተ ክርስቲያኖቻቸውና ለገዳሞቻቸው እንደዚሁም በጌታ መቃብር ውስጥ ሆነ በውጭ ፡ ጌታ ክርስቶስ በተወለደበት በቤተልሔምና በታላቁ ቤተ ክርስቲያን ፡ ቀጥሎም በዋሻው ሦስት ማዕዘናት ፡ ማለት በደቡብ ፡ በሰሜንና በምዕራብ ሆነው በይዞታቸው በሚገኙት በሮችና ቅዱሳት መካናት ሁሉ ተጠባቂነትና ደኅንነት ያገኙበታል ። ይኸ ውል በሀገሩ ለሚኖሩት ለሌሎቹ ክርስቲያን ዜጎች ማለት ለጆርጂያውያንና (ኩርዶች) ለኢትዮጵያውያን (ሐበሾች) እንደዚሁም ለመጐብኘት ለሚመጡት ኤውሮጳውያን ለኮፕቶች ፡ ለአርመኖች ፡ ለኔስቶራውያን ፡ ለያዕቆባውያንና የፓትርያርኩም ተከታዮች ለሆኑት ማሮኒታውያን ሁሉ በኅብረት ያገለግላል ። ሌሎቹም ዜጎች ሁሉ በታላቁና በደጉ ነቢይ በተወዳጁ የእግዚአብሔር መልእክተኛ ዘንድ ፡ በሕግ እንዲጠበቁና ደህንነትም እንዲያገኙ በእጁ ጽሕፈት በታዘዘላቸው መሠረት እኛ አማኞቹና ምእመናኖቹ ትእዛዙን አክብረን በሥነ ሥርዓት የምንጠብቃቸው ናቸው ። እላይ የተጠቀሰው ፓትርያርክ ግን ከሁሉም ይበልጥ ቅድሚያና የበላይነት መብት አለው ።

ሆኖም ሕዝቦቹ የመሬት ግብር ሆነ የዘበኛ አበል፡ እንደዚሁም ማናቸውም ሌላ ዓይ

ነት ቀረጥ እንዳይከፍሉ ነፃ አድርገናቸዋል ። ወደ ቅዱስ መቃብርም ሆነ፡ወደ ሌሎች ቅዱሳት መካናት ሲገቡ እንዲሁም በምድር ወይም በባሕር ሲጓዙ መንገላታት ወይም መከሰስ ሳይደርስባቸውና ሌላም ነገር ሳይጠየቁ በደህንነትና በሰላም እንዲኖሩ አድርገ ናል ። ቅዱስ መቃብሩን ለመጐብኘት (ለመሳለም) ተፈቅዶላቸው የሚገቡት ሌሎች ክር ስቲያኖች ግን እላይ ስሙ ለተጠቀሰው ፓትርያርክ ሚሶ የብር ድራሕም እያንዳንዳቸው ይከፍላሉ። ይኸ አዋጃቹን ፓትርያርኩ በሀገሩ ላይ ባለሙሉ ሥልጣን ገዢና ባለመብት ሆኖ እንዲያስተዳድር የሾምንበት ስለሆነ፡እያንዳንዱ አማኝ ወንድ ወይም ሴት እንደ ዚሁም ከእስላሞች ሰጋዲያን ወገን ባለጸጋ ወይም ድኻ የሆነ ሁሉ ወንድና ሴት ሳይ ቀር ትእዛዙን ለማክበርና ለመጠበቅ ይገደዳል። ይኸ አዋጃችን ታላላቆቹና የተከበሩት የነቢዩ ባልንጀሮች ማለት እነዓብዱላ ዑስማን ኢብን ዓፋን፡ስዒድ ኢብን ዜድ፡ዓብ ደልራሕማን ዒብን ዑፍና የቀሩትም ታላላቅና የተከበሩት ደቀ መዝሙሮቹ ባሉበት ታ ውጆ ተሰጠ ። ይኸ አዋጅ ሕጉን ባጸናንለት ሰው በኩል ተጠብቆ ክብር ያለውና የጸና ትእዛዛችን ሆኖ እንዲታወቅ አዘናል ።

ልዑል እግዚአብሔር መሐመድ ጌታችንን ከዘሮቹና ከደቀ መዝሙሮቹ ጋር ይባር ክልን፡የሁለቱ ዓለማት ጌታ ለሆነው እግዚአብሔርም ምስጋና ይድረሰው ። እግዚአብ ሔር ገገርአችን ነውና በረከቱ ከእንደራሴው ጋር ይሁን ።

፰ ራቢዕ አልዓወል፡በ፲፫ የነቢይ ሒጅራ ተጻፈ ።

ከዛሬ ጀምሮ እስከ ዕለተ ምጽአት ድረስ ማናቸውም አማኝ ይኸን አዋጃችንን አንብቦ ቢቃወም የእግዚአብሔርን ቃል-ኪዳን እንዳፈረሰና መልእክተኛውንም እንደ ተቃወመ ይቈጠርበታል ።

# ሁለተኛው ማስረጃ።

## ከሡልጣን ሱለማን የተሰጠ አዋጅ።

ሕያውና ቅዱስ በሆነው በአንድ አምላክ ስም፣ በኢየሩሳሌም የሚገኘው የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን በኢትዮጵያዊው አባ ሒኒስ ትጋት በ፲፫፻ ዓ-ም መታደስ ጀመረ። የማደሻውም ገንዘብ ከግርማዊ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና ከኢትዮጵያውያን ምእመናን ዘንድ የተላከ ነው።

ኢትዮጵያውያን ስለ ርስቶቻቸውና ስለ ገዳሞቻቸው ስለ ቅዱሳን ስፍራዎቻቸው፣ እንዲሁም በቅዱስ መቃብር ቤተ ክርስቲያን ውስጥና ውጭ ስላሉት ቤተ መቅደሶቻቸው ማስረጃ የሚሆኑ ፈርማዎችና አዋጅም የተነገረባቸው ሸሐኒ የተባሉ ንጉሣዊ ድንጋጌዎች በእጃቸው ይዘዋል። ከዚህም በላይ የኢትዮጵያውያን ይዞታ የራሳቸው መሆኑ የተረጋገጠ ሲሆን ስለ ሥርዓተ ጸሎታቸውና በተለይም በኢየሩሳሌም ስላለው ንብረታቸው ከዚህ በታች የተመለከተው ጽሑፍ ያስታውቅላቸዋል።

በመክነ ግንዘቱ ድንጋይ ላይ ሰባት ቀንዴሎች የሚንጠለጠሉበት ቦታ፣ በጌታ መቃብርም ውስጥ እሳት ከሚያቀጣጥሉበት ስፍራ፤ አንደኛው በደቡብ፣ አንደኛው በሰሜን ሆኖ ሌሎችም ሰባት ቀንዴሎች ከሚንጠለጠሉበት ቦታ፣ ከቤተ ክርስቲያኑ በስተደቡብ የሚገኙት ሦስት (ደጃፍ) የኢትዮጵያውያን በሮች ከነብርጭቆ መብራታቸው ሦስት (ደጃፍ) በስተሰሜን በሮች በድርብ ሳንቃ የተሠራው ክፍል፣ እላይ ከተጠቀሰው ቤተ መቅደስ በስተምሥራቅና በመክነ መቃብሩ መከከል ያለው መቅደስ በሳንቃ ታንጾ ከቅዱስ ትክል ድንጋይ በላይ ተገጥሞ የሚገኘው መዝጊያ ከነብርጭቆ መብራቱና ከነፍርግርጉ ሳንቃ መጋረጃው በሙሉ ጠቅልሎ የነርሱ ንብረት ስለሆነ ማንም በኢየሩሳሌም የሚገኝ ሌላ ክርስቲያን ማኅበር ከፍ ብሎ በተጠቀሱት ንብረቶች ላይ የሚቃወም አለኝ የሚል የለም።

ከዚህም ሌላ በስተደቡብ በኩል በቅዱስ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን የሚያጋናኝ ሆኖ በሩ በስተደቡብ በኩል የሚከፈተው ታችኛው የኢትዮጵያውያን ቤተ መቅደስና በመካነ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን በር በኩል የሚገባው የሡልጣን ገዳም (ዴር ሡልጣን) ከነቤቶቹና ከነመኖሪያዎቹ የኢትዮጵያውያን ንብረት ነው።

ልብሰ-ተክህኖ የሚቀመጥበት ትልቅ ሣጥን ከነይዞታውና በሡልጣኑም ገዳም (ዴር ኤል ሡልጣን) ላይኛው ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ያለው ንብረትና ብዙ መጻሕፍት በሙሉ፣ እንደዚሁም በሡልጣኑ ገዳም (ዴር ኤል ሡልጣን) አጠገብ የሚገኘው የቅድስት ኢሌኒ ቤተ ክርስቲያን ጭምር የነርሱ ነው።

ሡልጣን ሣሊም።

ይኸ ድንጋጌ በእጄ የተሠራ ቡሩክ ትእዛዜ ስለሆነና መጽናትም የሚገባው ስለሆነ ማናቸውም ሰው ሳይጠብቀው ቢቀር የእግዚአብሔር የቍጣ ሰይፍ ይወድቅበታል ።

የልዑል እግዚአብሔር ረድኤትና በተወደደው ነቢዩ ፣ የእግዚአብሔር ቅድስት ከተማ ወደሆነችው ወደ ኢየሩሳሌም ዛሬ በ፲፭ኛው ሰፈር በ፱፻፳፫ኛው የሒጂራ ዘመን በ፲፭፻፲፯ ዓ-ም ገብቼ ገዢ ሆኜ አለሁ ።

ስሙ እዚሁ ግርጌ የተመለከተው ክቡር የሸሪዓ ዳኛ ከእግዚአብሔር ዘንድ የመጽሐፍ ቅዱስ ሙሉ እውቀት እንዲሰጠው እየተመኘሁ ፣ ይኸንን እጅግ የተከበረውን ንጉሣዊ ድንጋጌ በኢየሩሳሌም በሚገኘው የሸሪዓ ፍርድ ቤት መዝገቡ እንዲመዘገብና ድንጋጌውም ጸንቶ የተከበረ እንዲሆን ያደርግ ዘንድ አዝዣለሁ ። በዚሁ ጊዜ የኢትዮጵያውያን እንደራሴ ማስረጃውን (መብቱን) በስፈለገ ጊዜ ሁሉ ለመከራከር እንዲችሉበት ተመዝግቦ እንዲሰጠው ጠይቋል ።

መስከረም ፲፭፻፵ ዓ-ም ተሠራ ።

ፊርማና የእማኞች ፊርማ
ሡልጣን ሱሌማን ።

## ከፎቶግራፍ የተቀዳ ነው ።

ይኸ ግልባጭ ከዚህ በታች ስማቸው የተዘረዘሩ ሰዎች ባሉበት ተሠጠ ፤

፩ኛ ከኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ገዳም — አባ ዓብደል መሲሕ ኢትዮጵያዊ ፤
፪ኛ ከግሪክ ኦርቶዶክስ ገዳም — ፓትርያርክ ጀማኖስ ጽርዓዊ ፤
፫ኛ ከአርመኖች ኦርቶዶክስ ገዳም — ማርኪስ አርመናዊ ፤
፬ኛ ከሸኽ ሙስተፋ ዘካርያ — የሸሪዓ ፍርድ ቤት ዳኛ ፤
፭ኛ ከሸኽ ኑር ኤዲንና ሐሰን ፓሻ — የጳለስጢና ጠቅላይ ገዢ ፤
፮ኛ ከክቡር ዳኛ ጀላቢ ኢብን አልባሕኒ — ከሸኽ መሐመድ ኢብን ኤልሸኽ ዓብደልቃድር አልሸሪፍ ኢብን አልሸኽ ሞሒ ኤዲን አልነካል ኤል ሻፊ — ሸኽ ኤል ኢስላምና የሃገር ቅድስት ሙፍት የነበሩት ፤
፯ኛ ከዛረሀ ሙስጣፋ ፓሻ ።

ከዋናው የቱርክ ጽሑፍ በትክክል የተቀዳ መሆኑን አረጋግጣለሁ ።

ማኅተም ዓ-ም

የኢየሩሳሌም እንደራሴና
ሰበት ሌላ ፊርማዎች ።

## ሦስተኛው ማስረጃ ።

### በኢየሩሳሌም የሸሪዓ ፍርድ ቤት ። — የመዝገብ ቁጥር ፻፶፭ — ገጽ ፯ ።

በታላቁ ጌታ ፊት የአዋቂዎች አዋቂ፣ የሕግ ትክክለኛ አስተርጓሚና ዋና አስፈጻሚ፣ በእስላሞች ዘንድ ትክክለኛ ዳኛ፣ በምድር ከፍተኛ ባለሥልጣን፣ የዕውቀትና የሐሳብ መፍለቂያ፣ የታላቁ ነቢይ ፍኖተ-ትምህርት ወራሽ፣ የዳኞች ዳኛ፣ የሕግ ባለሥልጣንና የዓለማዊው ችግር ፈች፣ የሐቀኝነት ገላጭ፣ እጅግ ከፍተኛና ገናና መንፈሳዊ፣ በሠለጠኑት ምድራውያን አካባቢዎች ዘንድ እጅግ የተሞገሰ፣ በእስላሞች ዘንድ የሸኾች ሊቅ፣ የተከለከለውና የሕጋዊው ምግባር ልዩ አዋቂ፣ የመልከምና የመጥፎ ነገር ሚዛን የሆነው የሸሪዓ ፍ/ቤት ዳኛ እጅግ የተከበረው ዓብደል ራሒም፣ በዚህ ውል ላይ ክንዱን ጭኖ ፈርሞበታል ። ክብሩና ሞገሱ ለዘለዓለም ይኑር ።

ዛሬ በኢየሩሳሌም የሚኖረው በግሪክ ክርስቲያኖች ፓትርያርክ በብፁዕ አባ ባይሶስ ፊት ቀርበ ክብረ መንግሥቱ ለዘለቄታው እንዲኖር የምንመኝለትን የተከበረውንና ከፍተኛ የሆነውን የሡልጣን ድንጋጌ (አዋጅ) ከማንተሙ ዘውድ ጋር አቀረበልን ። ትእዛዙም በከፍተኛው የእስላሞች ዳኛና በአንዱ አምላክ ብቻ በሚያምኑት ምእመናን ዘንድ ከፍተኛ ባለሥልጣን ሆኖ የከብርና. የሐቀኝነት ምንጭ እንደዚሁም ለሕዝብ ሁሉና ለኢየሩሳሌም ቃዲና፣ የሕግ አስከባሪ በሆነው ዳኛ አድራሽነት የተጻፈ ነው ።

ይኸ አዋጅ የወጣበት ምክንያት በኢየሩሳሌም ከተማ ውስጥ የሚኖሩት ያላመኑ የግሪክ ክርስቲያን ተወላጆች ከዚህ በታች የተጻፈውን አቤቱታ ለግርማዊ ንጉሥ ስለ አቀረቡ ነው ።

<u>አቤቱታ ።</u> ለሡልጣን አሕመድ ኻን ዋቅፍ እንዲከፈል የተወሰነብንን ግብር በመክፈል ረገድ ምንም ጉድለት ሳይኖርብንና፣ ከንጉሣዊው ድል ጊዜ ጀምሮ እስከ ዛሬ ድረስ ከፍተኛና የተከበሩ ትእዛዞች፣ የፍርድ መዝገቦችና (የሸሪዓ ሐጃ) የነቢዩም ታላላቅ ደቀ መዝሙሮች፣ በዘመኑ ማንም ሰው እንዳይከራከረን ያገዱበት ቃል-ኪዳን በእጃችን እያለ፣ በደማስቆ የሚገኙት ገዢዎችና ገንዘብ አስገቢ ሹማምንቶች (ደፍተር ዴር) ገንዘብ ከፈሉ እያሉ ግብር ሰብሳቢዎቻቸውን በየጊዜው ወደ ገዳሞቻችን ስለሚልኩብን ይኸ የገንዘብ አጠያየቃቸው ለሸሪዓውና (መንፈሳዊ ሕግ) ለፍትሐ ብሔሩ ሕግ፣ እንደዚሁም በደጉቹ በነቢዩ ደቀ መዝሙሮች ለተሰጠን ቃል-ኪዳን ተቃራኒ ሆኖ ብናል ። ከዚህም ሌላ የተጠቀሱት ገዢዎችና የደማስቆ ገንዘብ አስገቢ ሹማምንቶች ከአርባና ከሠላሣ ቀን በማይበልጥ ጊዜ እየመጡ እርዳታ ይጠይቁናል ። የተከለከለውን ገንዘብ ከሕግ ውጭ የሆነውን ፷ውን በአንድ አሰድ ፒያስተር ሒሣብ ከመቀበላቸው ሌላ ፴ውን ሕገወጥ ገንዘብ በአንድ አሰድ ፒያስተር ሒሣብ እንዲመነዘር ያደርጉብናል ። በአምስት ፒያስተር ብቻ የሚገዛውን ልብሰ-ደማስቆ ፴ ፒያስተር ሒሣብ ያስከፍሉናል ። አንድ ቀን ሰንዴ በገበያ ዓሥር መሥሪያ (ገንዘብ) ሲሸጥ እነርሱ ግን አንድ

ቍና ሁለት ፒያስተር ሒሣብ እንድንከፍላቸው ያስገድዱናል ። ይኸውም ሁሉ የሚፈጸምብን በኃይልና በዓመፅ ነው ።

እንደ ዘምዘም (የሜካ ምንጭ) አድርገን ወደምናስከብረው ወደ ዮርዳኖስ ወንዝ በየመቱ ለመጠመቅ ስንወርድ ፥ ከጥንት ጊዜ ጀምሮ በተለመደው መሠረት ለኢየሩሳሌም ገዢ በአንዱ ሰው ሦስት አሰድ ፒያስተር ሒሳብ እንከፍል ነበር ። አሁን ግን ከዚህ የበለጠ ምንም ተከፍሎ የማይታወቅ ሲሆን ከተለመደው በላይ ለመክፈል ይጠይቁናል ። ይኸውም በእያንዳንዱ ሰው ፬ ፒያስተር በተጨማሪ እንዲከፈል የሚጠይቅ ሲሆን ፥ ሌላም ብዙ የዓመፅና ሕገ-ወጥ ተግባሮች ይፈጽሙብናል ።

ይበልጡንም የግሪኮች ፓትርያርክ ከኸሊፋ ዑመርና (ነፍሱን ይማር) እንደዚሁም ከጥንታውያኖችና ከአሁኖቹ ሱልጣኖች ጊዜ ጀምሮ የወጡትን ንጉሣዊ አዋጆችና ጽኑ ሰነዶች እንዲሁም የውል ማስረጃዎችን የያዘ መሆኑ ስለሚታወቅ ለጆርጃውያንና (ኩርጆች) ለኢትዮጵያውያን (ሐበሾች) የተሰጡትን ርስቶች ጨምሮ ፥ በኢየሩሳሌም ቅዱስ መቃብር ቤተ ክርስቲያን ውስጥ የሚገኙትን የግሪኮች ቦታና ገዳማትን እንዲይዝና እንዲጠብቅ በዚህም ይዞታ ማንም ክርስቲያን ክፍል እንዳይከራከረን ታዞልን የኖረ ሲሆን አሁን የደማስቆ አገረ ገዢዎችና ግብር አስገቢ ሹማምንቶች በሚልኩብን ሠራተኞቻቸው ምክንያት የመብታችን ተቃዋሚዎች ሆነውብናል ።

ከዚህም በላይ በቅዱስ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን በቅዳሜ ስዑር ቀን እሳቱ ሲቀጣጠልና ብርሃን ሲወጣ ጡዋፎቹ ሲበሩ እንደልማዳችን ቀንዲል ይዘን ከአርመኖችና ከኤውሮጳውያን እንዲሁም ከሌሎቹ ክርስቲያኖች ሁሉ አስቀድመን በቤተ ክርስቲያኑ ዙሪያ መዞር (ዑደት ማድረግ) ልማዳችን ነው ። በቤተልሔም ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በተወለደበት ቦታ ላይ የሚገኘው የዋሻ ቤተ ክርስቲያን ፥ የደቡብና የሰሜን በር ቁልፎች እንዲሁም በዋሻው ውስጥ የሚገኙት ቀንዴሎችና መብራቶች ሌላም ቤተ ክርስቲያኑን የሚመለከት ሁሉ የአትክልቱና የመቃብሩ ቦታዎች ከግሪኮች በተቀር ሌላ ክርስቲያን አለኝ ብሎ የማይጠይቀው የግላችን ስለሆነ ፥ ግርማዊ ንጉሥ (ሱልጣን) ንጉሣዊ አዋጁን በማውጣት እላይ በዘረዘርነው መብታችን ሁሉ ማንም ሰው በማናቸውም ምክንያት እንዳይገባብን ያደርግልን ዘንድ በትሕትና እንለምናለን ።

<u>ትእዛዝ</u> ። የግሪክ ተወላጆች ከንጉሣዊ (ኻኒ) ድል ጊዜ ጀምሮ ነፃ የሆኑበትና እስከዛሬም ድረስ ማንም ሰው ቢሆን ሲከራከርበት ወይም ሁኔታውን በፍርድ አስተያየት ሊለወጥባቸው ያልቻለውን የታላቁን ሱልጣን አዋጆችና ታላላቁም የነቢዩ ደቀ መዝሙሮች የተስማሙባቸው የውል ሰነዶች ያሉዋቸው መሆኑን ተመልክተን ፥ ይኸንን ንጉሣዊ አዋጃችንን ስንሰጥ ማናቸውም ሰው በቀጥታ እንዲፈጽመው በማዘዝ ነው ።

በደማስቆ የሚገኙት አገረ ገዢዎችና ገንዘብ አስገቢ ሹማምንቶች (ደፍተር ዴር) እንደዚሁም ሌሎች ባለሥልጣኖች ወኪሎቻቸውን ወደ ግሪክ ተወላጆች እየላኩ ያለሕግ ገንዘብ ከመሰብሰብ እንዲከለከሉ እያስታወቅን ፥ በቅዱስ መቃብሩ ውስጥና በውጭ ቤትም ስፍራዎቻቸው እንዳይገቡባቸው አዝዘናል ። ከ፴ እና ከ፵ ቀን በማይበልጥ ጊ

ዜ ውስጥ የሚጠይቁዋቸውን እርዳታ ከልከለናል ። ፴ውን ሕገ-ወጥ ገንዘብ ስለ አንዱ አሰድ ፒያስተር ማስመንዘር የለባቸውም ፣ ኃይልና ዓመፅም በላያቸው ላይ መፈጸምና አምስት ፒያስተር የሚከፈልበትን ልብስ ፴ ፒያስተር ሒሣብ ማስከፈል የለባቸውም ። አሥር መስፈሪያ በቍና ስንዴ ሲከፈል ሁለት ፒያስተር ሒሣብ እንዳያስከፍሉዋቸውና ማናቸውንም ገንዘብ ያለ ሕግ በጭቆና እንዳይሰበስቡ አግደናል ።

እላይ የተጠቀሰው የቅዱስ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያንና ሌሎችም አብረው የሚገኙት የኢትዮጵያውያንና የጆርጂያውያን የርስት ቦታዎች የግሪክ ተወላጆች አብያተ ክርስቲያናትና ገዳማት ሁሉ ፣ በግሪክ ፓትርያርክ ሥርዓት ሆነው መጠበቅ ያለባቸው ሲሆን ፣ ወደፊት ማናቸውም በምትክነት የሚመጣ የግሪክ ፓትርያርክ ሁሉ ከከሊፋ ዑመርና (ነፍሱን ይማር) ከቀደምት ሱልጣኖች በተሠጡዋቸውና በተሠሩት የውል ማስረጃዎችና ስምምነቶች መሠረት መያዝ አለበት ። የግሪክ ፓትርያርክ ራሱ ወይም በወኪሉ ሥልጣን የጆርጂያውያንንና የኢትዮጵያውያኖችን ርስቶች አጣምሮ የሚጠብቅ ሲሆን ፣ ማንም የሌላ ሃይማኖት ወገን በዚህ ረገድ ሊከራከራቸው አይችልም ።

የግሪክ ተወላጆች (ሰሑት) የሃይማኖታቸውን ክብረ በዓላት እንደ ልማዳቸውና ታሪካቸው ሲፈጽሙ የደማስቆ አገረ ገዢዎችና ገንዘብ ሰብሳቢ ሹማምንቶች (ደፍተር ዳሪያ) ሊገቡባቸው አይችሉም ። ከዚህም ሌላ የቅዳሜ ስዑር መብራቶች በቤተ ክርስቲያኑ ውስጥ እንደልማዳቸው ሲቃጠልና ቀንዲሎችም ከበሩ በኋላ ቤተ ክርስቲያኑን ሲዞሩ ማንም አርመናዊ ሆነ ኤውሮጳዊ እንደዚሁም ሌላ ወገን ቀድሟቸው ሊዞር አይፈቀድለትም ። ይኸውም የቅዳሜ ስዑር መብራት ከበራ በኋላ በሚደረገው ክብረ በዓል አስቀድመው በቤተ ክርስቲያኑ ዙሪያ መዞር ልማዳቸውና መብታቸው ስለሆነ ነው ።

በቤተ ልሔም ጌታ ክርስቶስ በተወለደበት ላይ በእጃቸው በሚገኘው ዋሻ ምክንያት ማንም ሰው ሊቃወማቸው የማይችል ሲሆን ፣ በቤተ ክርስቲያኑም ደቡባዊና ሰሜናዊ በሮች የሚገኙት ቁልፎችና መቅረዞች ፣ መብራቶችና ሁለቱ የአትክልት ቦታዎች ሌላም በውስጡ የሚገኝና ቤተ ክርስቲያኑን የሚመለከት ሁሉ የነርሱ ነው ።

ይኸ አዋጃችን በሁሉም ዘንድ ታውቆ እንዲሠራበት ያወጣነው ስለሆነ ፣ የጦር ኃይሎች ጠቅላይ አዛዥ ከመኰንንኖቹና ከወታደሮቹ ፣ የሕዝብ መሪዎችና ነጋዴዎች እንደዚሁም ሌሎች ሁሉ ፣ የታላቁም የሱልጣን የወደብ ሹማምንቶችና (የአምሣ አለቆች ሲፓሒ ፣ ያንከርጃ) ፣ አገልጋዮች እንደዚሁም የማናቸው ሃይማኖት አበሎች ሁሉ በዚህ ረገድ ከግሪኮች ጋር ቢከራከሩና አቤቱታ ቢያቀርቡልን የማይለወጥ ትእዛዛችን መሆኑን እናስታውቃለን ።

ይኸ ታላቅ አዋጃችን ከዛሬ ጀምሮ የጸና እንዲሆንና የመብትም ማስረጃ ይሆን ዘንድ በግሪክ ተወላጆች እጅ እንዲቀመጥ አዘናል ።

በዚል ቃዕዳ ፲ኛ ቀን በ፳፻፹፱ ዓመት ላይ ተሠርቶ ተሰጠ ።

ከዚህም በኋላ የእግዚአብሔ በረከት እንዳይለየው የምንሻው ክቡር የሸሪዓ ፍ/ቤት ዳኛ ይኸንን ታላቅና ንጉሣዊ አዋጅ በኢየሩሳሌም በሚገኘው ሸሪዓ ፍ/ቤት መዝገብ

ቸው ውስጥ እንዲያሰፍሩና አዋጁም የጸና እንዲሆን ያደርጉ ዘንድ የታዘዙ ከመሆኑም በላይ ፣ የአርመን ወገኖች በክቡር ዳኛው በኩል ተጠርተው ከኢትዮጵያውያን ጋር ከመከራከር እንዲታገዱ ርስቶታቻቸውንም እንዲለቁላቸው እንዲደረግና ኢትዮጵያውያን (ሐበሾች) በንጉሣዊና በሱልጧን ሕግ መሠረት በያዙዋቸው ንብረቶች ምክንያት ያለ አገባብ እንዳይከራከሩዋቸው ማስጠንቀቂያ እንዲነገርላቸው ታዘአል ። ስለሆነም ክቡር የሸሪዓው ዳኛን ንጉሣዊው አዋጅ በተጠቀሰው መዝገብ ላይ እንዲመዘገብ ያኔ ውኑ አዘዙና ንጉሣዊውም አዋጅ በትእዛዙ መሠረት በኢየሩሳሌም ሸሪዓ ፍ/ቤት መዝገብ ውስጥ ሰፈረ ።

ወዲያው የተጠቀሱት ክቡር የሸሪዓ ፍ/ቤት ዳኛ ቀጥሎ የተመለከቱትን በለሥል ጣኖች ማለት የአርመኖች ጳጳስ ወኪል የሆኑትን ዶኒክና የአርመኖች አስተርጓሚ የሆነውን ያዕቆብ የሐይዘር ልጅን አቅርበው እላይ የተጻፈውን ንጉሣዊ አዋጅ በማንበብ ትእዛዙን አስታወቁዋቸው ።

ክቡርነታቸውም (ዳኛው) ንጉሣዊው አዋጅ የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያንና የግሪክ ቤተ ክርስቲያን ግንኙነት ያላቸው እንደመሆናቸው መጠን የግሪኮች ፓትርያርክ የኢትዮጵያውያንን ንብረቶች ጭምር የሚጠብቅና ማናቸውም ሌላ ሃይማኖት ወገን በዚህ ረገድ ጣልቃ ገብቶ ሊከራከር ወይም ሊያግዳቸው ያለመቻሉን ግልጽ አድርገው ከስረዱዋቸው በኋላ ፣ የኢትዮጵያውያን ንብረት የሆኑትን በመካነ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ የሚገኙትን ቅዱሳን በታዎችንና ፣ አንዱ መብራት በመካነ ግንዘቱ ድንጋይ ላይ የተንጠለጠለው ሆኖ ሰባቱ በቅዳሚ ስዐር እሳት ከሚያቀጣጥሉበት ክፍል ውስጥ የተንጠለጠሉ መብራቶቻቸውን በውስጣዊ ክፍል ውስጥ የሚገኘውን መቃብሩንና ከእሳቱ መቀጣጠያ ክፍል ውጭም አንድ ፣ በደቡብ አንድ በስሜን ያሉትን መብራቶች እንደዚሁም በቤተ ክርስቲያኑ ውስጥ የሚገኙትን ቅዱሳን መከናትን በሮችን ፣ መቅደሶቻቸውንና ንዋየ ቅዱሳን በእንጨት የተሠሩ ወለሎችን በሙሉ ለኢትዮጵያውያን እንዲያስረክቡ የአርመንን ወኪሎች አዘዙ ።

ቀጥሎም ከጎልጎታ ቤተ ክርስቲያን ውጭ የኢትዮጵያውያን ንብረትና መሰል የሆኑትን ገዳምና ንብረቶች ፣ መስቀሎች ፣ መጋረጃዎችና ንብረቶች በሙሉ ለኢትዮጵያውያን እንዲያስረክቡአቸው አዘውላቸዋል ።

የክቡር ዳኛው ትእዛዝ ትክክለኛና መልካም ስለ ነበረ ፣ አርመኖቹ ንጉሣዊውን አዋጅ በታላቅ ትሕትና የተቀበሉት መሆናቸውንና በታዎቹንና የቤተ ክርስቲያኑን መብራቶች ሙሉ በትእዛዙ መሠረት ለግሪክ ተወላጆች የሚያስረክቡ መሆናቸውን ገለጹና ፣ ግሪኮቹ ክቡር የሸሪዓው ዳኛ በመረጡዋቸው ዳኞች አማካይነት እላይ የተጠቀሱትን የብር መብራቶች ተረክበው ኢትዮጵያውያን በሚያሳዩት ጥንት በታቸው እንዲንጠለጠሉ ካግድረጋቸው በላይ ፣ በሮቹንና መቅደሶቹን እንደዚሁም ንዋየ-ቅዱሳቱን በሙሉ አስረከበዋቸዋል ።

ንጉሣዊው አዋጅ በታዛዥነት መፈጸሙን ለማስረዳትና ዝክረ ነገሩ እንዲታወቅ

ለማድረግ ያህል በሸሪዓው ዳኛ ታዘው ርክክቡን ያስፈጸሙት ዳኞች በዚሁ ቀን አንድ መዝገብ ከፍተው አፈጻጸሙን መዝግበዋል ።

ስለዚህ የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን በዚሁ ርክክብ መዝገብ ላይ ከተመዘገበው በስተቀር ሌላ የብር መብራቶች መስቀሎችና የብር ዕቃዎች በመከነ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን አለኝ ወይም ቀረብኝ የምትለው የለም ። አርመኖችም በንጉሥ ሡልጣን አዋጅ መሠረት ኢትዮጵያውያንና ግሪኮችን በሚመለከቱት ነገሮችና በኢትዮጵያውያን ርስቶች እንዲሁም በቤተ ክርስቲያኑ ውስጥና ውጭ በሚገኙት መብራቶቻቸው መንጠልጠያ ሰፍራዎች በቅዱሳን መካኖቻቸውና በንዋየ ቅዱሳታቸው የተነሣ ከግሪኮች ጋር እንዳይከራከሩ አዋጁ በሕግ ያገዳቸው መሆኑን በማስረዳት ክቡር የሸሪዓው ዳኛ አዝዘዋል ።

በዚል ሒጃ ፲ኛ ቀን በሺሕ ፺፮ የሑጁራ ዘመን ተሠርቶ ተሠጠ ።

ስለ ትክክለኛ ግልባጭ ፦

፳፱ የጆርዳን መንግሥት
ቴምብሮች ።

ራቢ አወል ፬ ቀን ፲፫፻፺፮ ሑጁራ ፤ — ፫-፲፩-፲፱፻፷፰ ዓ. ም.

ፊርማ ፡ ሒልሚ ሙሕታሲብ
የኢየሩሳሌም ሸሪዓ ፍ/ቤት ዳኛ ።

ማኅተም ፡ የኢየሩሳሌም ሸሪዓ ፍ/ቤት ዳኛ
ፊርማ ፡ ዋስፊ ቡዴሪ
ዋና ጸሐፊ ።

ከዋናው መዝገብ የተቀዳ ትክክለኛ ግልባጭ ስለመሆኑ ፤
የመዝገብ ቍጥር ፻፺፭ ፤ ገጽ ፯ ፤
ታኅሣሥ ፫ ቀን ፲፱፻፷፰ ዓ. ም.

ፊርማ ፡ ሙትላክ ሙሕታሲብ
ዋና ጸሐፊ ።

የመዝገብ መገልበጫ አንድ ዴናር በገንዘብ ደረሰኝ
(ቫውቸር) ቍጥር 3121/494683 ስለ መከፈሉ

ፊርማ ፡ ዋስፊ ቡዴሪ
ዋና ጸሐፊ ።

የኢየሩሳሌም ሸሪዓ ፍርድ ቤት ማኅተም ።

## አራተኛው ማስረጃ ።

ለክቡር ደጃዝማች መሸሻ በይ
በኢየሩሳሌም የኢትዮጵያ ጀኔራል ።

ክቡር ሆይ ፤

በኢየሩሳሌም ውስጥ በቅዱስ መቃብር ቤተ ክርስቲያን (ጎልጎታ) በስተምሥራቅ ገጥሞ ፡ የኢትዮጵያ መነኩሳት ስለሚኖሩበት ዴር ኤል ሡልጣን (ሡልጣን ገዳም) ስለ ተባለው ገዳምና ፡ ስለንብረትነቱም ባለቤትነት በኢትዮጵያ መነኩሳትና ኮፕቶች መከከል ስለ ተፈጠረው ክርክር ፡ ያለንን አስተያየት እንድንገልጽልዎ ተስፋ በማድረግ የጻፉት (የክቡርነትዎ) ደብዳቤ ስለ ደረሰን ፡ ቀጥሎ የተመለከተውን መልስ እናቀርባለን ።

የኢትዮጵያ መነኩሳት በጥንት ዘመን ወደዚሁ ገዳም የገቡበት ጊዜ አይታወቅም ፡ ይሁን እንጂ በሡልጣን ገዳም (ዴር ሡልጣን) አካባቢ ፡ በአቡነ አብርሃም ገዳም ውስጥ የሚገኘው ቤተ ክርስቲያን ግማሹና (ግማሹ የግሪክ ሆኖ ቀሪው በክርክር ያለው) የገዳሙ መሠረት ፡ በአቅራቢያው የሚገኘው ሜዳና (ኮፕቶች ለመስከቦች የሸጡት) ታችኛውም የውሀ ማጠራቀሚያ ጉድጓድ በኮፕቶችና በኢትዮጵያ መነኩሳት መከከል የክርክር ምክንያት ሆኖ ቢኖርም ፡ ሡልጣን ገዳም የተባለው (ዴር ኤል ሡልጣን) የኢትዮጵያ መነኩሳት ንብረት ነው ።

የዛሬ ፺፱ ዓመት የኮፕቶች መነኩሳት በኢትዮጵያውያን እጅ የነበረውን የሡልጣን ገዳም (ዴር ኤል ሡልጣን) መክፈቻ ባልታወቀ ምክንያት ከኢትዮጵያ መነኩሳት ወስደው ለኮፕቶች መነኩሳት እንዳስረከቡትና ከዚያም ጊዜ ጀምሮ የገዳሙ ንብረትና ይዞታ መብትነት በኢትዮጵያውያንና በኮፕቶች መነኩሳት መከከል የማያቋርጥ ክርክርና ችግር ፈጥሮ መኖሩንና በዚህም ክርክር ምክንያት በገዳሙ ውስጥ በሚገኙት ሁለት አብያተ ክርስቲያናት ይፈጸም የነበረው (የኢትዮጵያውያን) ክብረ በዓላትና ሥርዓተ ጸሎታት በኋለኞቹ ዓመታት ተቋርጦ መገኘቱን እናውቃለን ።

አክባሪዎ ነኝ
ፊርማ ፡ በኢየሩሳሌምና ዙሪያዋ
የግሪክ ፓትርያርክ
ማኅተም ፡ ዳሚያኖስ ፤

መስከረም ፯ ቀን ፲፻፲፰፻፷፩ ።

## አምስተኛው ማስረጃ ።

በእግዚአብሔር ስም በኢየሩሳሌም
የአርመን መንበረ ፓትርያርክ
ቁጥር ፱፻፺ ።

ለክቡር ደጃዝማች መሸሻ በይ
በኢየሩሳሌም የኢትዮጵያ ጄኔራል ።

ክቡር ሆይ ፣

በኢየሩሳሌም ውስጥ የሡልጣን ገዳም (ዴር ኤል ሡልጣን) በሚል ስም የሚጠራ ሆኖ ኮፕቶችና በኢየሩሳሌም የሚኖሩት የኢትዮጵያ መነኮሳት (አባቶች) ስለሚከራከሩበት የገዳሙ ንብረትነትና ይዞታ መብት ሐሳባችንን በደብዳቤ እንድንገልጽልዎ ክቡርነትዎ ጠይቆናል ።

የኢትዮጵያ መነኮሳት ዴር ኤል ሡልጣን (ሡልጣን ገዳም) በሚል ስም በሚጠራው ገዳም ውስጥ ከማናውቀው ከጥንት ጊዜ ጀምሮ ሰፍረው ይኖራሉ ። የገዳሙም መክፈቻ ካለፉት አርባ ዓመታት ወዲህ በኮፕቶች መነኮሳት እጅ የቆየ ቢሆንም በምን አኳኋን ወደ እነርሱ እጅ እንደተላለፈ የማናውቀው ነገር ነው ።

ከዚህም ይበልጥ መክፈቻው ወደ ኮፕቶች ከገባበት ጊዜ ጀምሮ የገዳሙ ባለንብረትነትና የይዞታው መብት እንዲታወቅላቸው የኢትዮጵያ መነኮሳት ሳያቋርጡና ሳይሰለቹ የሚከራከሩበት መሆኑንና እስከ አለፉት ጥቂት ዓመታት ድረስም መንፈሳዊ ክብረ በዓላትንና የተለመደ የዘወትር ሥርዓተ ጸሎታትን በክርክሩ ምክንያት ከመፈጸም ያቋረጡ መሆናቸውን ጭምር እናውቃለን ።

የክቡርነትዎ አክባሪ ነኝ
በኢየሩሳሌምና ዙሪያዋ
የአርመን ፓትርያርክ
ማኅተም ።

መስከረም ፲፬ ቀን ፲፱፻፷፩ ።

# ALOISIUS PICCARDO

MISERATIONE DIVINA ET APOSTOLICÆ SEDIS GRATIA

EPISCOPUS TITULARIS CAPHARNEI

VACANTE SEDE HIEROSOLYMITANA

VICARIUS GENERALIS

ETC.

Io sottoscritto, Vicario Capitolare Amministratore del Patriarcato Latino di Gerusalemme, fondato sulla testimonianza di Anziani della popolazione Latina di questa Città, fo fede e testifico che il Convento degli Abissini, oggetto del conflitto tra questi ed i Cofti, è ab antiquo in disposizione e quindi possesso degli Abissini, poichè in esso hanno sempre abitato e fatto le loro preghiere con tutte le loro cerimonie ecclesiastiche.

In fede ecc.

Gerusalemme, dal Patriarchio Latino, li 10 Ottobre A. del S. 1905



ስድስተኛው ማስረጃ ።

አሎኢሲዩስ ፒካርዶ
በእግዚአብሔር ምሕረትና በሐዋርያ ጸጋ
ጳጳስ (ኤጲስቆጶስ) ዘቅፍርናሆም

በኢየሩሳሌም የክፍቱ ወንበር
ጠቅላይ እንደራሴና አስተዳዳሪ ።

እኔ ከዚህ በታች የፈረምኩ በኢየሩሳሌም የላቲን መንበረ ፓትርያርክ ጠቅላይ እንደራሴና መልእክተኛ ይኸንን በኢየሩሳሌም በሚኖሩት ላቲናውያን ሽማግሌዎች ቃል የተመሠረተውን ምስክርነት ስሰጥ፣ ኢትዮጵያውያን በገዳሙ ምክንያት ከኮፕቶች ጋር ሲከራከሩ የኖሩ ከመሆኑም በላይ ኢትዮጵያውያን ይኸንን ገዳም ከጥንት ዘመን ጀምሮ ይዘውት የኖሩና ሥርዓተ ጸሎታቸውንና ሌላም ማናቸውንም መንፈሳዊ ሥርዓታት ሲፈጽሙበት የኖሩ መሆናቸውን በዚህ ምስክርነቴ አረጋግጣለሁ ።

በኢየሩሳሌም የላቲን መንበረ ፓትርያርክ
ፊርማ፡ አሎኢሲዩስ ፒካርዶ
ጠቅላይ እንደራሴና አስተዳዳሪ፤
የጽሕፈት ቤቱ ማኅተም ።

ጥቅምት ፲ ቀን ፲፱፻፸ ።

## ሰባተኛው ማስረጃ ።

بطركية الموارنة
القدس

PATRIARCAT MARONITE
Jérusalem

58

Jérusalem le ............ 190

Je soussigné rends témoignage d'après les documents trouvés dans nos archives, que le couvent de Deir El Soultan est propriété des Abyssins; et depuis quinze ans que je suis à Jérusalem j'ai toujours vu et entendu que le dit couvent de Deir El Soultan est leur propriété et habité par eux, j'ai même assisté à leurs offices religieux dans les deux chapelles qui se trouvent dans le passage conduisant de leur couvent de Deir El Soultan au parvis du St Sépulcre

Jérusalem le 25 Août 1905

[illegible]

J. El. Moualleum
Chorévêque de Jérusalem
vicaire Patriarcal Maronite



## ሰባተኛው ማስረጃ ።

የማሮናይት መንበረ ፓትርያርክ
በኢየሩሳሌም ።

እኔ ከዚህ ግርጌ ላይ የፈረምሁ በኢየሩሳሌም የማሮናይት ጳጳስ በእጃችን በሚገኙት መዛግብት መሠረት እንደሚታወቀው ሁሉ፣ ዴር ኤል ሱልጣን (ሱልጣን ገዳም) የተባለው ገዳም የኢትዮጵያውያን ንብረት መሆኑን እመሰክራለሁ። በኢየሩሳሌም ከተቀመጥኩበ ቸው ካለፉት ፲፭ ዓመታት ጀምሮ ኢትዮጵያውያን የተጠቀሰውን ገዳም የግል ንብረት አድርገው በመያዝ ወትሮም የሚኖሩበት መሆኑን ከመስማቴም ይበልጥ በዓይኔም አይቼ አለሁ ። ከዚህም በላይ መንፈሳዊ ክብረ በዓሎቻቸውን ከዴር ሱልጣን (ሱልጣን ገዳም) ወደ ቅዱስ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን ምድረ ግቢ በሚያስገቡት ሁለት ቤተ መቅደሶቻ ቸው ውስጥ ሲያከብሩና ሥርዓታተ ቅዳሴም ሲፈጽሙ አብሬ ያከበርኩ መሆኔን አረ ጋግጣለሁ ።

ፊርማ፣ ጂ. ኤል. ሙዓሊም
በኢየሩሳሌም የማሮናይት ጳጳስና
የማሮናይት መንበረ ፓትርያርክ እንደራሴ
የመንበረ ጵጵስናው ማኅተም ።

በነሐሴ ፳፭ ቀን ፲፱፻፭ ተሰጠ ።

ስምንተኛው ማስረጃ ።

ለክቡር ደጃዝማች መሸሻ በይ
በኢየሩሳሌም የኢትዮጵያ ጀኔራል ።

ክቡር ሆይ ፤

በኢየሩሳሌም ዴር ሡልጣን ተብሎ በሚጠራው ገዳም ምክንያት በኢትዮጵያና በኮፕት መነክሳት መከከል ስለ ተነሣው የገዳሙ ንብረትነት ክርክር፤እንዲሁም በገዳሙ ውስጥ ስለሚገኙት ሁለት ቤተ ክርስቲያናትና ስለ በሩ ቍልፍ የምናውቀውን ያኽል ማስረጃ እንሰጥዎ ዘንድ የጠየቁበት ጽሑፍ ደርሶናል ።

በእኛ ዘንድ እንደሚታወቀው ሁሉ ዴር ሡልጣን ተብሎ የሚጠራው ገዳም ከጥንት ዘመን ጀምሮ በኢትዮጵያውያን እጅ የቆየና በውስጡም መንፈሳዊ ሥርዓቶቻቸውን ሲፈጽሙበት የኖረ መሆኑን ስንገልጽልዎ ፤ የበሩ ቍልፍ ወደ ኮፕቶች የገባበት ዘዴ ፤ ዘመንና ቀን ፤ እንዲሁም ኢትዮጵያውያን እላይ በተጠቀሱት ሁለት አብያተ ክርስቲያናት ውስጥ ይፈጽሙዋቸው የነበሩትን ክብረ በዓላትና ሥርዓተ ጸሎታት ሁሉ ያቋረጡበትን ምክንያት ግን የማናውቀው መሆናችንን በዚህ ደብዳቤአችን ለማስረዳት እንወዳለን ።

ይኸ ማስረጃ በሚገባ የተሰጠ ስለ ሆነ የክቡርነትዎን ትእዛዝ ለመቀበል ይጠባበቃል።

የክቡርነትዎ ነኝ
በኢየሩሳሌም የጥንታዊው የሶርያ ገዳም ጳጳስ
ፊርማ ፤ ኤልያስ
ማኅተም ።

ዛሬ መስከረም ፲፬/፲፱፻፷ ዓ. ም.

PAT. ARM. CAT. JÉRUSALEM
بطركخانة الأرمن الكاثوليك
القدس

Je soussigné rends témoignage que depuis les trente cinq ans que je suis à Jérusalem comme vicaire patriarcal, j'ai toujours vu le Couvent Dit, Deir es Soultan, propriété des Abyssins et habité par des Abyssins, J'ai vu aussi que les Abyssins célébraient toujours leurs offices religieux dans les deux petites chapelles, l'une de St. Michel et l'autre des quarante Martyrs qui sont situées dans le passage par lequel on descend du couvent Deir Es Soultan à l'atrium du Saint Sépulcre Il peut y avoir environ vingt cinq ans de la

Jérusalem. 28 Août 1905

Isachin Cousmayan
Abbé mitré, vicaire pat. armenien catholique

[illegible]





# ዘጠነኛው ማስረጃ ።

## የአርመን ካቶሊካዊ ፓትርያርክ እንደራሴ
## በኢየሩሳሌም ።

እኔ እዚሁ ግርጌ የፈረምሁ፣የፓትርያርክ እንደራሴ ሆኜ ባለፉት ፴፭ ዓመታት በኢየሩሳሌም ውስጥ ስቀመጥ ዴር ሡልጣን የተባለው ገዳም የኢትዮጵያውያን ንብረትና ይዞታ መሆኑን አውቃለሁ ። ከዚህም በላይ ኢትዮጵያውያን ከዴር ሡልጣን ገዳም ወደ ቅዱስ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን ምድረ ግቢ በሚያስገባው መተላለፊያ (ከሪ ዶር) በሚገኙት ሁለት ትንንሽ ቤተ መቅደሶቻቸው ማለት በቅዱስ ሚካኤልና በአርባዓ ሰማዕታት፣ ፀቱ እንስሳ፣ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ መንፈሳዊ ሥርዓቶቻቸውን ሲፈጽሙና ሲያከብሩ ያየሁዋቸው መሆኔን እመሰክራለሁ ።

ሥርዓተ ጸሎቱ ለ፹፭ ዓመት ያህል በዚሁ ዓይነት ተከብሯል ።

በኢየሩሳሌም የካቶሊካውያን አርመኖች
የፓትርያርክ እንደራሴ
ፊርማ፣ ዮአቂም ተመያን ።

ነሐሴ ፳፫ ቀን ፲፱፻፭ ዓ. ም.

## አስረኛው ማስረጃ ።



64

Il sottoscritto Padre Filippo Rizzi, Residen-
te Custodiale di Terra Santa, attesta e fa fede che nei
primi ventiquattro anni di sua permanenza a Gerusa-
lemme, cioè fino all'anno 1893, i Religiosi France-
scani di Terra Santa passarono per la porta che
dalla IX^a Stazione mena al piazzale della Basi-
lica del SS.mo Sepolcro e che la detta porta ve-
niva loro aperta dai Monaci Abissini.

Scritto per la verità.

Gerusalemme, S. Salvatore 5 Ottobre 1905

F. Filippo Rizzi Presidente Custodiale

[illegible]

# አሥረኛው ማስረጃ።

## ሞኖግራም ።

እኔ ከዚህ በታች የፈረምሁ የሀገር ቅድስት ጠባቂ ፊሊፖ ሬቼ ፣ ለ፴፱ ዓመት በኢየሩሳሌም ውስጥ የቅድስት ሀገር ጠባቂ ሆኜ እ. ኤ. አ. እስከ ፲፱፻፹፫ ዓ. ም. መጨረሻ ድረስ ስሠራ ፣ የፍራንሲስካን ካህናቶች ከፍኖተ መስቀሉ ዘጠነኛ ምዕራፍ ወደ ቅዱስ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን አጥር ግቢ ለመግባት ሲጓዙ ፣ ከጥንት ጊዜ ጀምሮ በኢትዮጵያ መነኮሳት እጅ ሲከፈት በኖረው በር በኩል ወደ ተጠቀሰው መካነ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን ሲገቡ መኖራቸውን በዚህ ጽሑፍ እያረጋገጥሁ ፣ እውነተኛ ምስክርነቴን ሰጥቻለሁ ።

መድኃኔ ዓለም ገዳም ኢየሩሳሌም
ፊርማ ፣ አባ ፊሊፖ ሬቼ
የሀገር ቅድስት ተጠባባቂ አስተዳዳሪ፣
ማኅተም ።

ጥቅምት ፳ ቀን ፲፱፻፹ ዓ. ም.

## እሥራ አንደኛው ማስረጃ ።

እኔው ከዚህ በታች የፈረምሁት የሰማንያ አምስት ዓመት ሽማግሌ፣ ስመ እግዚአብሔርን በመጥራት ምዬ በትክክል ስለማውቀው ነገር ሁሉ፣ ከዚህ በታች የተመለከተውን የምስክርነት ቃሌን እሰጣለሁ ።

የዛሬ ስድሳ ዘጠኝ ዓመት ልክ፣ በሟቹ በኢብራሒም ፓሻ በመጀመሪያው ዘመን ቡበኒክ የተባለ ተላላፊ በሽታ (ፈራ) በኢየሩሳሌም ስለ ገባ፣ በዴር ሡልጣን ገዳም ውስጥ ከሚኖሩት ኢትዮጵያውያን መካከል አንድም ሳይተርፍ በሙሉ በበሽታው ተነድፈው አልቀው ነበር ። በዚህም ዘመን ውስጥ አገሩን ያስተዳድር የነበረው የቱርክ መንግሥት በተጠቀሰው ሕመም የተነደፉትን በሽተኞች የሚያስቀምጥበት ሥፍራ በማጣት ችግር ስለ ገጠመው፣ በሽተኞቹን በሙሉና በተለይም እላይ በተጠቀሰው ገዳም አቅራቢያ የሰፈሩትን የላቲን ገዳም ነዋሪዎች ወደ ኢትዮጵያውያን ገዳም ገብተው እንዲያርፉ አስገድዶአቸው ነበር ።

ይሁን እንጂ በሽታው እስቲበርድና ከበረደም በኋላ እላይ የተጠቀሰው የኢትዮጵያውያን ገዳም ለአርባ ቀን ያህል ተለቆ፣ ሰውን ከመግባት የሚያግድ አንድም ኢትዮጵያዊ በሌለበት ሰዓት፣ ሙሰ ጣኑስ ጐርጐር የተባለው ብልጥ ሰው ኰፕቶች በገዳሙ ውስጥ ገብተው ሰፈሩን እንዲይዙ አድርጎ ነበረና፣ ኢብራሒም ፓሻ ከሞተም በኋላ ብዙ ኢትዮጵያውያን ሲመጡ ገዳማቸው በኰፕቶች ተይዞ ስላገኙት ኰፕቶችን ያላንዳች ጭቅጭቅና ክርክር በኃይል አስወጥተው ገዳማቸውን እንደገና ያዙ ።

እኔም በዕድሜ ሽማግሌ እንደመሆኔ መጠን ስለ መሰከርኩት ቃል ሁሉ እርግጠኛ ከመሆኔም በላይ፣ ይኸ ምስክርነቴ እውነተኛና የተረጋገጠ ለመሆኑ በኔ ዕድሜ ልክ በሚገኙት ሰዎች ዘንድ ሁሉ የታወቀ ነው ። ከዚህም ሌላ ኰፕቶች አንድ ሰው በሚሞትባቸው ጊዜ ሬሳውን በኢትዮጵያውያን ገዳም በኩል ለማሳለፍ ቢጠይቋቸው፣ ኢትዮጵያውያን ኰፕቶችን ይከለክሏቸው ስለ ነበር፣ በሁለቱ ወገኖች መካከል ጠብ ሲነሣ መኖሩን ከማወቄም በላይ፣ የቅዱስ መስቀል በዓል በሚከበርበትም ቀን ወደ ኢትዮጵያውያን ገዳም እየሔድን በዓሉን ስናከብር መኖራችንን እመሰክራለሁ ።

በእግዚአብሔር ስላለኝ ፍቅር ይኸን ምስክርነቴን ዛሬ መስከረም ፩ ቀን ፲፱፻፳፩ ዓ. ም. ላይ ሰጠሁ ።

ስለ እውነተኛ ምስክርነቴ
ፊርማ፣ ፍራንሲስ እስጤፋን ።

እኛ ከዚህ በታች ስም ስማችንንና ማኅተሞቻችንን ያስቀመጥን ሰዎች፣ ከዚህ በላይ ፍራንሲስ እስጤፋን የሰጠው የምስክርነት ቃል እውነተኛና ትክክለኛ መሆኑን ስመ እግዚአብሔርን ጠርተን እንመሰክራለን ።

መስከረም ፫ ቀን ፲፱፻፳፩ ዓ. ም. ።

የምስክሮች ፊርማና ማኅተም፣

ዩሰፍ ጡማ አወድ፣ ናጂብ ሐበሽ፣ ራፋል ማርኩስ፣ አንቶን አሎንዞ፣ ሚካኤል ዒሣ፣ ማቲያ ሐላቅ፣ ሐና አንቶን ሚኬል፣ ሚካኤል ዩሰፍ ሚኬል፣ ዒሳ ዩሰፍ ሐበሽ፣ ጂብራን ዒሳ ሐበሽ፣ ሐና ያስሚናህ፣ አንቶን ዓብደል መሲሕ፣ አልፎንስ አንቶን አሎንዞ፣ ዩሰፍ ዓብደል መሲሕ፣ አንቶን ዩሰፍ ማርኩስ፣ ዩሰፍ ፈራን፣ ያዕቆብ ቀዛዝ ሹክሪ እስጤፋን፣ ፍራንሲስ በትሩስ ሐላቅ፣ ሙብረክ ኸሊል ሐና፣ ሚካኤል ዓብደ መሲሕ፣ ክለመንስ አሎንዞ፣ ኤልያስ ቃዛዝ፣ ዓብዱላ ኒኮላ፣ ቢሽራ አቡ ዒሳ፣ ፍራንሲ ከማር፣ ሐና ያዕቆብ ርዝቀላህ፣ ማርቲን አንቶን ታርሽ፣ ፍራንሲስ ካራም፣ ሲምዖን አ ቶን ሐላቅ፣ የ፹፪ ዓመት ሽማግሌና፣ ሌሎች ስድስት ፊርማዎች ።

## እምሬ ሁለተኛው ማስረጃ ።

ለተወደዳችሁ ወንድሞቻችን ፡ በኢየሩሳሌም የግሪክ ኦርቶዶክሳዊት ማኅበር አባሎች ።

በኢየሩሳሌም ከተማ አጥር ግንበኛ ውስጥ የሚገኘው ዴር ሱልጣን የተባለው የኢትዮጵያውያን ገዳምና ፡ እንዲሁም በዚሁ ገዳም ውስጥ ሆነው ወደ ቅዱስ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን መግቢያ ወለል የሚያስወጡት ሁለት አብያተ ክርስቲያናት ይዞታችንና ርስታችን ፡ እንደዚሁም ንብረታችን ስለ መሆን አለመሆናቸውን የሚያረጋግጥ እውነተኛና ንጹሕ ምስክርነታችሁን እንድትሰጡን በትሕትና እየለመንን እግዚአብሔር ዘለዓለማዊ ሕይወት እንዲሰጣችሁ እንመኝላችኋለን ።

ቴምብርና ፊርማ ።

መልስ ።

ከዚህ በላይ የጻፉችሁልንን ጥያቄ አንብበን ጉዳዩን በሙሉ የተረዳነው መሆናችንን እንገልጽላችኋለን ። ዴር ሱልጣን የተባለው የኢትዮጵያውያን ገዳምና በውስጡ ሆነው ወደ ቅዱስ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን (መግቢያ) ወለል የሚያስወጡት ሁለት አብያተ ክርስቲያናት ከጥንት ዘመናት ጀምሮ በኢየሩሳሌም የሚኖሩት የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ መነኮሳት ርስትና ንብረት ሆነው መኖራቸውንና ፡ ኢትዮጵያውያኖችም በተጠቀሱት ሁለት አብያተ ክርስቲያናት ውስጥ በዓሎቻቸውን ሲያከብሩና የሃይማኖት አገልግሎታቸውን ዘወትር ሲፈጽሙባቸው የኖሩ መሆናቸውን በዚህ ምስክርነታችን እናረጋግጣለን ።

ፊርማ ፡ በኢየሩሳሌም መንሺያ ቀበሌ ውስጥ
የግሪክ ገዳም ሙኽታር
ጀርየስ ዓጣ ኻታብ ፡ መንሱር ሚኪኤል ፡ ሐና ዘናኒሪ
እና ሌሎች ፲፪ የማኅተም ፊርማዎች ።

## አሥራ ሦስተኛው ማስረጃ ።

ለተወደዳችሁ ወንድሞቻችን
የአርመን ገዳም አባሎች በኢየሩሳሌም ።

በኢየሩሳሌም ከተማ አጥር ግንቦች ውስጥ የሚገኘው ዴር ሡልጣን የተባለው ገዳምና በውስጡ ሆነው ወደ ቅዱስ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን መግቢያ ወለል የሚያስወጡት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች፣ ከኛ በስተቀር ሌላ በአለኝታ የሚገባበቸው እንደሆነ ወይም ደግሞ የኛ የግል ንብረቶች እንደሆኑ ለይቶ የሚያረጋግጥ ምስክርነታችሁ እንዲሰጠን በትሕትና እየለመንን ፣ እግዚአብሔር ዘለዓለማዊ ሕይወት እንዲሰጣችሁ እንመኝላችኋለን ።

ቴምብርና ፊርማ ።

መልስ፤

ከዚህ በላይ የጻፋችሁልንን ጥያቄ አንብበን ጉዳዩን በሙሉ ተረድተነዋል ። ዴር ኤል ´ሐበሽ (የኢትዮጵያውያን ገዳም) በሚል ስም የሚጠራው ገዳምና፣ በውስጡም ሆነው ወደ ቅዱስ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን መግቢያ ወለል የሚያስገቡት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ከጥንት ዘመናት ጀምሮ እስከዛሬ ድረስ በኢትዮጵያውያን እጅ የኖሩ የገዳሙ ንብረት መሆናቸውን እንመሰክራለን ።

ፊርማ፣ ያዕቆብ ዋኒስ መረሽሊ
የአርመን ገዳም ሙኽታር ።

ስምዖን ያዕቆብ፤ ፊሊፕ ጂሪየስ፤ ይስሐቅ ከራበይድ ኤልብሮቲ፤ ፊጃዶር ኢብራሂም በይታር፤ ያዕቆብ ሐስቢያን፤ አብከር ኢብን ዩሰፍ ኤልበና፤ ጋራበድ ጂሪየስ ወርታን፤ ግልኩን ኢብን ኤልያስ፤ ሐና ጂሪየስ ወርተን፤ ሚናስ ያዕቆብ፤ ሚናስ ኢብን አንቶን፤ ሚናስ ኢብን መከር፤ ኪቮርከ ይስሐቅ፤ ኢብራሂም ያዕቆብ፣ ጋራበድ ሚከኤል ጡማ፤ ቱሉማን ሚከኤል ከንጂ፤ ጋራበድ ወኒስ ወርተን፤ ሐና ኢብን ጂሪየስ ከዕባሽ፤ ኢብራሂም ይስሐቅ፤ ያዕቆብ ወኒስ መረሽሊ፤ ቦጎስ አዋደሲያን፤ ጋራበድ ወኒስ ዘካሪያን፤ ግከርዲች ኢብን ሚናስ፤ ያዕቆብ ካብላኒያን፤ ኪቮርከ ጋራበድ ኤል ሙብየድ፤ ሙራድ ጋራበድ ጡማ፤ አርቲን ኢብን ዩሰፍ ኤልበና፤ ሉኪያስ ወኒስ ኤል መረሽሊ፤ ኢብራሂም በዱያን፤ ዳዉድ ጂሪየስ ኩካ፤ ፊጃዶር ወኒስ ማርጋሪያንና ወሐን ዩሰፍ ኤልበና ።

## አሥራ አራተኛው ማስረጃ ።

ለተወደዳችሁ ወንድሞቻችን
የላቲን ገዳም አባሎች - ኢየሩሳሌም ።

በኢየሩሳሌም አጥር ግንቦች ውስጥ የሚገኘው ዴር ሡልጣን የተባለው የኢት ዮጵያውያን ገዳምና በውስጡም የሚገኙት ወደ ቅዱስ መቃብሩ (ጎልጎታ) ቤተ መቅ ደስ መግቢያ ወለል የሚያስወጡት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ፣ በእጃችን የሚገኙና ንብረቶቻችን መሆን አለመሆናቸውን በመግለጽ ትክክለኛና ንጹሕ ምስክርነታችሁን እንድትሰጡን በትሕትና እየለመንን ፣ እግዚአብሔር ዘለዓለማዊ ሕይወት እንዲሰጣ ችሁ እንመኝላችኋለን ።

ቴዎብርና ፊርማ ።

<u>መልስ፤</u>

ከዚህ በላይ የጻፋችሁልንን ጥያቄ አንብበን ጉዳዩን በሙሉ ተረድተነዋል ። ዴር ሡልጣን በሚል ስም የሚጠራው የኢትዮጵያውያን ገዳምና በውስጡም የሚገኙት ወደ ቅዱስ መቃብሩ (ጎልጎታ) ቤተ መቅደስ መግቢያ ወለል የሚያስገቡት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ከጥንት ዘመናት ጀምሮ በኢየሩሳሌም በሚገኙት የኢትዮጵያ ኦር ቶዶክስ መነኩሳት እጅ የኖሩ ንብረቶቻቸው መሆናቸውንና፤ በተጠቀሱትም ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ውስጥ የሃይማኖት አገልግሎታቸውን ሲፈጽሙባቸው የኖሩ መሆ ናቸውን እንመሰክራለን ።

ፊርማ ፣ ጂሊል ሎሬንስ
በኢየሩሳሌም የጣልቢያ ቀበሌ ሙኽታር (የጭቃ ሹም)፤

ጂብራኤል ዒሳ ሐበሽ፤ ሐና ፋህሚ እንዲሪያ፤ ሚልሔም ኢብራሂም ንምር፤ ሐና አንቶን ሚኬል፤ ዩሰፍ ሚናወል ጋንዱራ፤ አንቶን ሐና ማናወል፤ ፊድል እላሀ ዒሳ ኤል አሽከር፤ ዩሰፍ ፓስካል አልቢና፤ ፍራንሲስ ዩሰፍ ከራም፤ ክለሜንት አሉንዘ፤ ዩሰፍ ጂርየስ ጋታስ፤ ከሊል ከሸ፤ ዒሳ ሐና ከሊስ፤ አዩብ አቡ ኢምራን፤ ሐና ሲምዖን ሐዳድ፤ ፍራንሲስ ጡማ ኤቤስ፤ ዩሰፍ ሐና ሰላሕ፤ ዒሳ ዩሰፍ ከራም፤ ጂብራኤል ዩሰፍ ከራም፤ አንቶን ዳውድ ኤል ኩርዲ፤ ሐና አንቶን ባውሎስ፤ ስምዖን ያዕቆብ አንድሪያ፤ ጡማ ዒቤስ፤ ሐና ፍራንሲስ ባውሎስ፤ ሚከኤል ዒሳ ሐበሽ፤ አንቶን ዩሰፍ አልቢና፤ ሉትፊ ሐና ሐበሽ፤ ዩሰፍ ዒሳ ኒስናስ፤ አንቶን በውትሮስ ዶብለህ ።

ሌሎች አርባ ፊርማዎችና ማኅተሞች ።

## እሥራ አምስተኛው ማስረጃ ።

በኢየሩሳሌም የአጥር ግንቦች ውስጥ ዴር ሡልጣን በሚባለው ገዳማችን አዋሳኝ በይስሐቅ ቤይ ሕንፃ ውስጥ የምትኖሩ የተወደዳችሁ ልጆቻችን ሆይ !

በኢየሩሳሌም የሚኖሩት የኮፕቶች አርቶዶክሳዊ ገዳም አባሎች ሥርዓተ ጸሎታቸውን ለማድረስ ዑደት ሲያደርጉ ሆነ ! ወይም ሰው ሞቶባቸው ሥርዓተ ፍትሐት ሲፈጽሙ ፣ በገዳማችን በኩል አቋርጠው የማለፍ ልምድ ወይም መብት ያላቸው መሆን አለመሆናቸውን የሚያረጋግጥ ትክክለኛና እውነተኛ ምስክርነታችሁን እዚሁ ግርጌ እንድትሰጡን በትሕትና እየለመንን ፣ እግዚአብሔር ዘለዓለማዊ ሕይወት ይስጣችሁ ዘንድ እንመኛለን ።

ፊርማ ፣ መምህር ፊቃደ
የኢትዮጵያ አርቶዶክስ ገዳም አበምኔት
ኢየሩሳሌም ።

ጥር ፳፮ ቀን ፲፱፻፮ ዓ·ም

እጅግ ለተከበሩ መምህር ፊቃደ
በኢየሩሳሌም የሚገኘው የኢትዮጵያ አርቶዶክስ ገዳም አለቃ ።

ክቡር አባታችን ሆይ !

ከዚህ በላይ የጻፉልንን ጥያቄዎ አንብበን ጉዳዩን ተመልክተነዋል ። ዴር ሡልጣን የሚባለው ገዳማችሁ አዋሳኝ በሚገኘው በይስሐቅ ቤይ ሕንፃ ከኖርንበት ጊዜ ጀምሮ ! የኮፕቶች አርቶዶክሳዊ ገዳም አባሎች መንፈሳዊ ክብረ በዓላትን ለማክበር ዑደት ሲያደርጉ ሆነ ወይም ሥርዓተ ፍትሐት ሲፈጽሙ በተጠቀሰው ገዳማችሁ በኩል አቋርጠው ሲያልፉ ፈጽሞ አይተናቸው የማናውቅ መሆናችንን በእውነትና በትክክል እንመሰክራለን ። የኮፕት ጳጳስ በዓመት አንድ ጊዜ በቅዳሜ ስዑር ቀን ብቻ እላይ በተጠቀሰው ገዳም በኩል አልፎ የሚሄድ መሆኑን እናውቃለን ።

ይኸ እርግጠኛ ምስክርነታችን መሆኑን እንመሰክራለን ።
ጥር ፳፯ ቀን ፲፱፻፮ ዓ·ም

ፊርማዎች ፦

እንቶን ሙሳ ቀማር ፤ ዘካሪያ ሐበሽ ፤ እስክንድር ቀማር ፤ ጁብራን ኒኮላ ፤ ሰሌም ዩሰፍ ሲንዮራ ፤ ያዕቆብ ኒኮላ ፤ ቢሽራ ዓዩብ ፤ ዓብዱላ ኒኮላ አንድሪያ ፤ ባትሮስ ባውሎስ ፤ ሚካኤል ዳውድ ነጃር ፤ ይስሐቅ አተላሕ ፤ ዩሰፍ እንቶን መሲሒ ፤ ስምዖን ሲንዮራና ፣ ሌሎችም ፊርማዎች ።

# አሥራ ስድስተኛው ማስረጃ ።

تصريح بالقسم

انا الموقع بذيل هذا التصريح يعقوب ابراهيم الفاعود من رام الله اصرح بالقسم بان الاسم المذكور اعلاه اسمي وان التوقيع المبين ادناه توقيعي وان جميع ما هو مذكور فـي هذا التصريح صحيح وموافق للواقع .

ان لي من العمر الان حوالي (٧٥) سنة وكان والدي قد عين واسطه لدير الروم في غرفتين من املاك دير الروم في القدس وكانت والدتي اذ ذاك تذهب الى دير السلطان فـي القدس وهو في الناحية الشرقية للقيامه ويقع على سطح مغارة الصليب وكنت اذهب مع امـي الى دير السلطان المذكور لانها كانت تشتغل عند الرهبان والراهبات الاحباش في ذلـك الدير فتطحن لهم حمص وفول وتقوم باعمال من هذا القبيل . ومنذ ستة وخمسين سنة تقريبا وكان عمري اذ ذاك سبعة عشر او ثمانية عشر سنة فتح الاقباط الباب الشمالي لدير السلطان المذكور بالقوة وجرت بين الاقباط والاحباش معركة وفي النتيجة تمكن الاقباط من فتح الباب المذكور وكان قبل ذلك عبارة عن فتحه صغيره فهدموا ووسعوا هذه الفتحة حتى صارت بابا وهو الباب القائم الان ووضع الاقباط على هذا الباب الذي فتحوه بلاطه مكتوب عليها كتابة وتاريخ لا ادري ما هو ولكن دير الروم تدخل وذهب ترجمان بطريرك دير الروم ومعه القواس المسمى ابو ناصيف الشامي وتولا عبده فازالوا هذه البلاطه وكسروها . لقد كنت في ذلك الوقت اشاهد الرهبـان والراهبات الاحباش يصلون في الكنيستين المعروفتين بكنيسة الملاك وكنيسة الاربع حيوانات وكذلـك كنت اشاهد تجنيز الرهبان الاحباش الذين يتوفون في هاتين الكنيستين وكانوا يمارسون الطقوس الدينية الاخرى فيهما بحرية تامة دون معارضة احد وكان اخراج الرهبان الاموات بعد تجنيزهم في الكنيستين المذكورتين يتم الى ساحة القيامة وعندما فتح الاقباط الباب الشمالي بالقوة علـى الوجه المذكور منعوا الاحباش من الصلاة في الكنيستين المذكورتين وقد استمر الاحباش في اخراج موتاهم من الباب الجنوبي الذي يفتح غربا المؤدي الى ساحة القيامة دون معارضة .

المصرح بالقسم

يعقوب ابراهيم الفاعود من رام الله

صرح به مقسما بالله العظيم ووقعه بتوقيعه
امامي يعقوب ابراهيم الفاعود من رام الله
في هذا اليوم [illegible] من شهر نيسان سنة ١٩٥٤
حاكم الصلح



## እሥራ ስድስተኛው ማስረጃ ።

## የመሐላ ምስክርነት ።

እኔ ከዚህ በታች የፈረምሁ የራምላህ ተወላጅ ያዕቆብ ኢብራሒም ኤል ቃዑድ ሁሉን በሚችል እግዚአብሔር ስም ምዬ እንደሚከተለው እመሰክራለሁ ።

ከዚህ በላይ የተጻፈው ስም ፥ ስሜ ነው ፥ ከግርጌ የሚገኘውም ፊርማዬ ነው ። በጽሑፉም ላይ የሰፈረው ሐተታ በሙሉ እውነተኛና የተረጋገጠ ምስክርነቴ ነው ።

ዕድሜዬ አሁን ፹፭ ዓመት ነው ። ከዕለታት አንድ ቀን አባቴ ስለታመመ የግሪክ ገዳም ማኅበሮች በኢየሩሳሌም ገዳማቸው ውስጥ ከሚገኘው ሕንፃ ሁለት ክፍል ቤት ለማረፊያ ሰጥተውት ነበር ። በዚህ ጊዜ እናቴ በኢየሩሳሌም ውስጥ ከመካነ መስቀሉ ዋሻ በላይ ካለው ከቅዱስ መቃብሩ ጎልጎታ ቤተ ክርስቲያን በስተ ምሥራቅ ወደሚገኘው ዴር ሡልጣን እየሔደች በገዳሙ ውስጥ ለሚኖሩት ለኢትዮጵያ መነኮሳትና መነኮሳይያት ጥራጥሬ በመፍጨትና ሌላም ይህን የመሳሰለ በመሥራት ታገለግል ስለ ነበረ ፤ እየተከተልኋት ወደ ዴር ሡልጣን እሔድ ነበርሁ ።

የዛሬ ፳፭ ዓመት ልክ የ፲፯ እና የ፲፰ ዓመት ልጅ በነበርሁ ጊዜ ፤ ከፕቶች በዴር ሡልጣን የሚገኘውን ሰሜናዊ በር ሲከፍቱ አየሁ ። ይኸም በር ከዚያን ጊዜ በፊት ትንሽ መሽሎኪያ ስለ ነበረ ፥ እነርሱ ግንቡን በማፍረስ መሽሎኪያ የነበረውን ሥፍራ ትልቅ በር እንዲሆን አደረጉት ። በሩም እስከ ዛሬ ድረስ ያው የፊቱ ሆኖ ይታያል ። ይኸውም ከሆነ በኋላ ክፕቶች አሁን ቀኑን ለይቼ ለማስታወስ በማልችልበት ጊዜ ከበሩ ጉብን ላይ አንድ ዓይነት ጽሑፍ ያለበት ሰሌዳ አኑረውና ሰክተው ስለ ነበር ፥ የግሪክ ገዳም ሰዎች ነገሩን በመቃወማቸው የተነሣ ፥ የግሪኩ ገዳም ፓትርያርክ አስተርጓሚ የሆነው አቡ ነሲፍ ኤልሻሚ ከመዶሻ ያዢውና ፤ ኒኮላ ዓብዱ ከተባለው ሽማግሌ ጋር አበታው ድረስ ሄዶ የድንጋዩን ሰሌዳ አውርዶ ሰባብሮታል ።

ከዚህም ሌላ በዚያን ዘመን የኢትዮጵያ መነኮሳትና መነኮሳይያት በሁለቱ ቤተ ክርስቲያኖች ማለት በመልአኩ ቤተ ክርስቲያንና በአርባዕቱ እንስሳ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ የሃይማኖት አገልግሎታቸውን ሲፈጽሙ ከማየቴም በላይ ፤ በተጠቀሱት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ውስጥ የሙታን ፍትሐትና ሌላም ሥርዓተ ቅዳሴ ማንም ከልካይ ወይም ተቃዋሚ ሳይኖራቸው በሙሉ ነፃነት ሲፈጽሙና ሲያከብሩ በዓይኔ አይቻለሁ ።

የመነኮሳትም ሬሳ ሥርዓተ ፍትሐት በተጠቀሱት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ተፈጽሞ ሲያልቅ ወደ ቅዱስ መቃብሩ (ጎልጎታ) ቤተ ክርስቲያን ምድረ ግቢ በኩል እየተወሰደ ይቀበር ነበር ።

ከዚህም ይልቅ ከፕቶች ከፍ ብሎ በተመለከተው አኳኋን ሰሜናዊውን በር በኃይል

ሀ) በኢየሩሳሌም ፴፰ ዓመት ጊዜ ስኖር የኢትዮጵያ መነኮሳት በዴር ኤል ሱልጣን ገዳም ውስጥ ሲኖሩ አይቻለሁ ፤ እንዲሁም የተባሉት መነኮሳት በአርባዕቱ እንስሳ ቤተ ክርስቲያንና በቅዱስ ሚካኤል ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ከ፳፰ ዓመት ጊዜ ጀምሮ እስከ ነሐሴ ፳፫ ቀን ፲፱፻፭ ዓ. ም. ድረስ የሃይማኖት አገልግሎታቸውን ሥርዓት ሲፈጽሙ አይቻለሁ ፤ ይላል ።

፮ የላቲን ፓትርያርክ ቫይካር ጀኔራል በኢየሩሳሌም የሰጡት መልስ ፤ በሰነድ ቁጥር ፮ ላይ ተዘርዝሮ ይገኛል ፤ መልሱም ፤ —

ሀ) የላቲን ሽማግሌዎች በሰጡት ምስክርነትና ራሴ ባገኘሁት መሠረት ፤ ዴር ኤል ሱልጣን የኢትዮጵያውያኖች ርስት ነው ፤

ለ) እንዲሁም የኢትዮጵያ መነኮሳት ከገዳሙ አቅራቢያ በሚገኙት ቤተ ክር ስቲያኖች ውስጥ ሥርዓተ ቅዳሴ ይፈጽሙ ነበር ፤ ይላል ።

፯ የመካነ ቅዱስ ጠባቂ አባ ፊሊፖ ሬቼ ከዚህ በላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ፤ ሰነድ ቁጥር ፲ ላይ የሰጡት መልስ ፤ —

ሀ) በኢየሩሳሌም ከ፳፬ ዓመት ጊዜ ጀምሮ በዚሁ ሥራ ስሠራ ነበር ፤

ለ) የፍራንሲስካን መነኮሳት በዚሁ ጊዜ ውስጥ ከ፱ኛው የመስቀል ጉዞ ቦታ ወደ ቅዱስ መቃብር ሜዳ በሚወስደው በር ሲተላለፉ አይቻለሁ ፤

ሐ) የደቡባዊውን በር ቍልፍ በዚያን ጊዜ በኢትዮጵያውያን መነኮሳት እጅ ይገኝ ነበር ይላል ።

፰ ፍራንሲስ እስጤፋን በመጽሐፉ ሰነድ ቍጥር ፲፩ ላይ የሰጡት መልስ ፤ —

ሀ) ይህንኑ የምስክርነት ቃል ስሰጥ ዕድሜዬ ፹፰ ዓመት ነው ፤

ለ) ከፕቶች በተስቦ በሽታ ምክንያት የኢትዮጵያ መነኮሳት ሁሉ ካለቁ በኋላ የዴር ኤል ሱልጣን ቍልፍ በእጃቸው አግብተዋል ፤

ሐ) ኢብራሂም ፓሻ (ማለት በዚያን ጊዜ የግብጽ ገዢ የነበረው) ከፕቶች ቍልፉን እንዳይዙ ረድተዋቸዋል ፤

መ) ኢብራሂም ፓሻ ከሞተ በኋላ አንዳንድ ኢትዮጵያውያኖች ወደ ኢየሩሳ ሌም መጥተው ገዳማቸውን መልሰው በእጃቸው ያለክርክር ለማግባት ቻሉ ፤

ሠ) አንድ ከፕት መነኩሴ በሞተ ጊዜ ከፕቶች በኢትዮጵያውያኖች ገዳም በኩል የቀብሩን ሥርዓት ለመፈጸም ለማለፍ ሲጠይቁ ኢትዮጵያውያኖቹ ይከለክሉዋቸው ነበር ፤

ረ) ይህ ሁናቴ እያሌ የኢየሩሳሌም ሽማግሌዎች የሚያውቁት ነው ፤ ይላል ።

፱ የግሪክ ኦርቶዶክሳውያን ሙክታር በኢየሩሳሌም ጆርጅስ ዓጣ ኩታብ ፤ ማንሱር ሚኬልና ሐና ዘናኒሬ በተባለው መጽሐፍ ፤ ሰነድ ቁጥር ፲፱ ላይ የሰጡት መልስ ፤ —

ሀ) ዴር ኤል ሱልጣን የኢትዮጵያውያኖች ንብረት ነው ፤

ለ) ከገዳሙ አጠገብ የሚገኙት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች የኢትዮጵያውያኖች ንብረት ሆነው ኢትዮጵያውያኖቹም የቤተ ክርስቲያንን ስነ ሥርዓት ይፈጽሙበት ነበር ፡ ይላል ።

፲ በኢየሩሳሌም የሚገኙት አርመኖች ፡ በሰነድ ቍጥር ፲፫ ላይ የሰጡት መልስ ፡ —

ሀ) ዴር ኤል ሱልጣንና አጠገቡ የሚገኙት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች የኢትዮጵያ መነከሳት ናቸው ይላል ።

፲፩ በኢየሩሳሌም የሚገኙት የላቲን ሰዎች ፡ በሰነድ ቍጥር ፲፬ ላይ የሰጡት ምስክርነት ፡ —

ሀ) ዴር ኤል ሱልጣንና አጠገቡ የሚገኙት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች የኢትዮጵያውያኖች ንብረት ናቸው ፤

ለ) የኢትዮጵያ መነከሳት የቅዳሴ ስነ ሥርዓት በሁለቱ ቤተ ክርስቲያኖች ውስጥ ሁለ ጊዜ ይፈጽሙ ነበር ፡ ይላል ።

፲፪ ሽማግሌው ያቆብ ኢብራሂም ኤል ካውድ ፡ በሰነድ ቍጥር ፲፯ ላይ የሰጡት ምስክርነት ፡ —

ሀ) ይህንን ምስክርነት ስሰጥ ዕድሜዬ ፹፫ ዓመት ሆኖ ገና በሕይወቴ የምገኝ ሰው ነኝ ፤

ለ) እናቴ በዴር ኤል ሱልጣን ውስጥ ለኢትዮጵያውያን መነከሳት ታገለግል ነበር ፤

ሐ) በሕይወቴ ጊዜ ውስጥ ክፕቶች የሰሜኑን በር በኃይል ሲከፍቱት አይቻለሁ ፡ ድሮ በሩ ትንሽ ቀዳዳ ብቻ ነበረው ፤

መ) ክፕቶቹ በስተሰሜኑ በር በላይኛው ክፍል አንድ የድንጋይ ጽሑፍ ካስቀመጡ በኋላ ፡ የግሪክ ፓትርያርክ ድንጋዩን እንዲያነሡ አዘዙዋቸው ፡

ሠ) ከገዳሙ አጠገብ በሚገኙት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ውስጥ የኢትዮጵያ መነከሳት ሥርዓተ ቅዳሴ ሲፈጽሙ አይቻለሁ ፤

ረ) ኢትዮጵያውያኖቹ ወደ ቅዱስ መቃብር ቤተ ክርስቲያን በሚወስደው በገዳሙ ደቡብዊ በር በኩል ሙታውያኖቻቸውን ሲያሳልፉ አያቸው ነበርሁ ፡ ይላል ።

ከዚህ በላይ የተዘረዘሩት ማስረጃዎች ከዚህ ቀደም ካቀረብናቸው ማስታወሻዎች በተጨማሪነት የቀረቡ ናቸው ።

ስለዚህ ኢትዮጵያውያኖቹ ክቡር ኮሚሲዮኑ ከዚህ ቀጥሎ የተዘረዘረውን ጕዳይ እንዲፈጽምላቸው በማክበር ያመለክታሉ ፡

፩ የዴር ኤል ሱልጣን ገዳምና አብረውት ያሉት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ንጉሣዊው ትእዛዝ በተሰጠበት ጊዜ በነበሩበት አኳኋን እንዲመለሱ ፡ የተባለው ንጉሣዊው ትእዛዝ በዚል ቂዕዳ ፡ ፲፱፻፶፱ ዓመተ ሄጂራ የተሰጠ ነው ። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ የተፈጸሙት ግፎችና አገባብ የሌላቸው ተግባሮች ሁሉ ሕገ ወጥ ተብለው እንዲቈጠሩ ፤

፪ ከፕቶች በ፲፰፻፷፰ እና በ፲፰፻፺ ዓመተ ምሕረት ውስጥ የፈጸሙዋቸው ሕገ ወጥ ተግባሮች ሁሉ ንጉሣዊውን ትእዛዝ ተቃዋሚዎች ተብለው እንዲቈጠሩ፣

፫ ዴር ኤል ሱልጣን ሁለ ጊዜ በኢትዮጵያ መነኮሳት እጅ የነበረና ርስታቸው መሆኑን ተገልጾ ቁልፎቹንም ለኢትዮጵያውያኖች ተመላሽ እንዲያደርጉ አንድ ውሳኔ እንዲሰጥ፤

፬ የተባሉት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ቁልፎች እንደዚሁ ለኢትዮጵያ መነኮሳት ተመላሽ እንዲሆኑና እንዲሁም የቤተ ክርስቲያኖቹ መብት ከታወቀ በኋላ ማናቸውም ሰው በተባለው ገዳም በኩል እንዳይተላለፍ የተከለከለ መሆኑን መወሰን፤

፭ ኢትዮጵያውያኖቹ በተባለው ገዳምና ቤተ ክርስቲያኖች ላይ ያላቸውን መብት እንዲታወቅላቸው ደጋግመው ሲጠይቁ በመኖራቸው ምክንያት ማናቸውም የይርጋ ሕግ ሊያግዳቸው የማይችል መሆኑን መወሰን፤

፮ ስለ ገዳማችን ውሳኔ የሚሰጥበት መሠረት የአማራይት ቃል ኪዳንና እንዲሁም የሱልጣን ሰሊምና የሱለይማን ትእዛዞች መሆናቸውን መወሰን ።

ክቡር ኮሚሲዮኑ ጉዳዩን አብራርቶ ከተመለከተ በኋላ፣ተገቢ የሆነ ትክክለኛ ውሳኔ እንደሚሰጠን በመተማመን አስቀድመን ምስጋናችንንና የማክበር ሰላምታችንን በትሕትና እናቀርባለን ።

ፍጹም አክባሪዎ፣
አ ባ ፊ ል ጶ ስ
የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን
ጳጳስ በኢየሩሳሌም ።

እስታቱስኩ፤ከሚባለው መስተር ካስት ከጻፈው መጽሐፍ የተቀዳ ከእንግሊዝ
ጳጳስ ዘንድ የመጣልኝ፡ ፲፱፻፵፭ ዓ-ም ጥቅምት ፲ ቀን
አባ ፊልጶስ።

## የዴር ኤል ሡልጣን ገዳም፣

የዴር ኤል ሡልጣን ገዳም ከጎልጎታ ቤተ ክርስቲያን ጋር በስተምሥራቅ የሚዋ ሰን ነው፤ይህ ገዳም በገረገራው መኻከል አንድ ጉልላትና=ዶም=የመነከሳት መኖሪያ የሆኑ ጐጆዎች ኖሮት በኮፕት ዘበኛ ይጠበቃል፡ ጉልላቱም የቅድስት እሌኒ መቅደስ መብራት ነው፡ ገዳሙ የሚገኘው በ፲፪፻፵፭ ዓ. ም. በክርስቲያኖች ወረራ ጊዜ በፈረ ሰው አሁንም የፍራሹ ምልክት በሚታይበት ጥንት የአውጉስጢን ቀሳውስት መዘዋ ወሪያ በነበረው ሥፍራ ላይ ነው፡ ወደ ጎልጎታ በሚወስደው መታላለፊያ በሩ የሚከ ፈተው የቅዱስ ሚካኤል መቅደስና የአርባዕቱ እንስሳ መቅደስ ከገዳሙ ጋር የተያ ያዙ ናቸው።

ኮፕቶችና ኢትዮጵያውያን በየበኩላቸው ዴር ሡልጣን የሚባለው ገዳም የየራሳችን ነው ይላሉ፡ ኮፕቶች ግን በዚያ የሚገኙትን ኢትዮጵያውያን በእንግድነት እንደተቀ በሏቸውና በእነሱ ፈቃድ ብቻ እንዲቆዩ እንጂ ባሰቤቶች እንዳይደሉ አድርገው ይናገ ራሉ፤ የክርክሩም ታሪክ በጣም ረጅምና የተሳሰረ ነው፡ የኢትዮጵያና የኮፕት ቤተ ክርስቲያን እምነት አንድ ሆኖ የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን የአሌክሳንድርያው የመን በረ ማርቆስ ልጅ ሆኖ ሁል ጊዜም የሚሾምላት ሊቀ ጳጳስ ከኮፕት ሊቃውንት መከ ከል በመሆኑ ይህ በሁለቱ መኻከል ያለው ክርክር በተለይ የሚያሳዝን ነው።

እያሌ የመኻከለኛው መቶ ዘመናት ደራሴዎች የኮፕቶችና የኢትዮጵያውያኖች "የኖ ቢያ„ መነከሳት በጎልጎታ አከባቢ እንደነበሩ ሲመሰክሩ ኢትዮጵያውያን በመከን ቅዱ ሳት ከፍ ያለ መብት እንደነበራቸው ያረጋግጣሉ፡ በአሥራ አራተኛው መቶ ዓመት ትንሽዋ የግብፅ ቅድስት ማርያም መቅደስና ደግሞ በአሥራ እምስተኛው መቶ ዓመት በመዘዋወሪያው የሚገኘው የተድላ መቅደስ በኢትዮጵያውያን እጅ ነበረ፡በአሥራ ሰባ ተኛው መቶ ዓመት ግን እንደሌሎች ታናናሽ የክርስቲያን ኮሙኒቲዎች ሁሉ የቱርክን ገገር ግብር መክፈል ስለ እቃታቸው ቤተ ክርስቲያኑ ራሱ ተወሰደባቸው እነሱ እንደ ሚሉት እስከዛሬ በእጃቸው ያለውን የዴር ሡልጣንን ገዳም ብቻ ይዘዋል።

ኮፕቶች ደግሞ በበኩላቸው ዴር ሡልጣን የተባለው ገዳም ምን ጊዜም የራሳ ቸው ንብረት እንደነበረና የሃይማኖት ጓደኞቻቸው የሆኑት ኢትዮጵያውያን ንብረታ ቸው ተወርሶ ማረፊያ ባጡ ጊዜ በርኅራኄ እንዳስጠጉአቸው ይናገራሉ።

በእንደዚህ ያለው ሁናቴ በአርባዕቱ እንስሳ መቅደስ እንዲጸልዩ ተፈቅዶላቸው ስለ ገዳሙ የተነሣው ክርክር ለመጀመርያው ጊዜ ባለፈው መቶ ዓመት ተሰማ፡እስከዚህ ጊዜ ድረስ ፀንቶ የተቋቋመው ድርጅት እንደምን እንደተናጋና በመከናት ቅዱሳት ጉ

ዳይ እኒህ ሁለት እንትማማች ቤተ ክርስቲያናት የቅርብ ጓደኞች በመሆን ፈንታ በምን
ምክንያት እንደተጣሉ በግልጽ አይታወቅም ፤ ኢትዮጵያውያን ከዴር ሡልጣን ገዳም
በተባረሩ ጊዜ በጥቅምት ፲፯-፲፰፻፳ ዓ. ም. በቃዲው የተጻፈ የነበራቸውን ዝርዝር የሚያ
ሳይ ጽሑፍ በኮፕቶች እጅ ይገኛል ፤ በዚሁ ጊዜ በመንግሥት ፈቃድ ገዳሙን እንዲያ
ሳድሱ የሚያስረዱ አራት ወይም አምስት ጽሑፎች ለማቅረብ ይችላሉ ፣ ገዳሙን መያ
ዛቸውን የሚጠቅስ ቀደም ብሎ የተጻፈ አንድ ጽሑፍ ደግሞ በእጃቸው ይገኛል ።

በ፲፰፻፴፰ ዓ. ም. እጅግ የሚያስፈራ ተስቦ በሽታ በኢየሩሳሌም ገብቶ ስለነበረ
ኢትዮጵያውያን ሁሉ ብሙሉ አለቁ ይባላል ፤ ይኸውም የሆነው ኢብራሂም ፓሻ ኢየ
ሩሳሌምን በያዘበት ጊዜ ስለሆነ ፣ የኢትዮጵያውያንን ጽሑፎችና ቤተ መጻሕፍት የንብ
ረት ክርታቸውንም ጭምር ተላላፊ በሽታ ነክ አስመስለው በማቅረብ ለማቃጠል የፓ
ሻውን ፈቃድ አግኝተው ኮፕቶች በዚህ አጋጣሚ ሳይጠቀሙበት የቀሩ አይመስልም ፤
ደግሞም የቤተ ክርስቲያናትንና የገዳሙን ቊልፍ መፍቻዎች እጃቸው ለማግባት
ቻሉ ፣ የኒህ የሁለት ኮሚኒቲዮዎች ክርክር በአሥራ ዘጠነኛው መቶ ዓመት መላው ቢቀጥ
ልም ኢትዮጵያውያን በ፲፰፻፵፫ ዓ. ም. የቊልፍ መፍቻውን እጃቸው ያገቡ ይመስላል ።

የቱርክ መንግሥት ምርመራ አድርጎ የሰጠው ብይን ኮፕቶችን የሚደግፍ ነበር ፣
ኢትዮጵያውያንም የቊልፍ መፍቻውን አንሰጥም በማለት እምቢ ስለአሉ ሌሎች ቊል
ፎች ተበጅተው መፍቻቸው ለኮፕቶች ተሰጠ ፣ ይኸውም የሆነው አጼ ቴዎድሮስ ከታ
ላቋ ብሪታንያ ጋር ግጭት ባደረጉበት ጊዜ ስለነበረ ኢትዮጵያውያንን በደላቸው ።

ኮፕቶች የሰሜኑን በር እንዲያሰሩ ማዘጋጃ ቤት በ፲፰፻፶፱ ዓ. ም. ሲፈቅድላቸው
ሁለተኛው ግጭት ተደረገ ፣ ኮፕቶች መላው የሰሜኑን ግድግዳ ለማፍረስ ፈልገው ነበ
ር ፣ ነገር ግን በይርጋ ደምብ መሠረት የቱርክ መንግሥት ከለከላቸው ፣ ኢትዮጵያው
ኖችም ኮፕቶች አንዳች መለዋወጥ ለማድረግ መብት የላቸውም ሲሉ በብርቱ ከመቃ
ወማቸው ሌላ የኮፕቱን ሊቀ ጳጳስ ዘለፉዋቸው በዚህም ምክንያት ኢትዮጵያውያን ከጥ
ንት ጀምሮ በአርባዕቱ እንስሳ መቅደስ ለመጸለይ የነበራቸውን መብት ኮፕቶች ከለ
ከሏቸው ።

ጉዳዩ ለቱርክ መንግሥት ቀርቦ ስለ ነበረ መቅደሱን ለኢትዮጵያውያን እንዲከፍቱ
ላቸው ኮፕቶች ሳያስገድዳቸው ቀረ ፣ ሆኖም ኢትዮጵያውያን ለራሳቸው ብቻ የሚያገ
ለግል በር በገዳሙ በስተምሥራቅ ግድግዳ እንዲከፍቱ ፈቀደላቸው ፣ በዚህም ጊዜ ም
ንም እንኳን ኮፕቶች በብርቱ ቢቃወሙ ኢትዮጵያውያን የፋሲካን ጸሎታቸውን የሚ
ያደርሱበት ድንኳን በገዳሙ ጣሪያ ላይ እንዲተክሉ ተፈቀደላቸው ።

ከዚህ አድላዊ ውሳኔ በኋላ ኢትዮጵያውያን ምንም ያህል ትግላቸውን ቢያጠነክሩ ፣
የቱርክ መንግሥት በዚህ አስቸጋሪ ጉዳይ ኮፕቶችን በመደገፍ ስለ አዘነበለ ምንም ሊያ
ደርጉ አልቻሉም ።

ከዚህም በስተቀር ኢትዮጵያውያን የሚጠይቁት ንብረት የራሳቸው መሆኑን የሚ
ደግፍ ጽሑፍ ማስረጃ ሊያቀርቡ ከቶ አልቻሉም ።

የኢትዮጵያውያን ጽሑፍ ማስረጃዎች ሁሉ በ፲፰፻፴፰ ዓ. ም. እንደተቃጠሉ ከዚህ በላይ ተነግሯል ፣ ሆኖም እኒህ ማስረጃዎች በኢትዮጵያ ይገኛሉ የሚል ታሪክ እየገነነ ሄደ ፣ የማስረጃዎችም መኖርና አለመኖር የፈጠረው መጠራጠር የውጭ አገር መንግ ሥት በነገሩ እንዲገባ አጋጣሚ ጊዜ ሆነ ፣ መስኩብ በመከናት ቅዱሳት ያላትን ምኞት ለመዘርጋት ይህ አጋጣሚ ጊዜ ሆኖ ስለ አገኘችው ኢትዮጵያ እንዲመለስላት ከምትጠይ ቀው ንብረት በከፊል እንድታገኝ መገበባት ከተደረገ በኋላ የኢትዮጵያን ጥያቄ ደገፈች፤ ስለዚህም በ፲፰፻፺፫ ዓ. ም. በመስኩብ አምባሳደር ጠያቂነት የዶር ኤል ሡልጣን ገዳም ጉዳይ እንደገና እንዲመረመር የቱርክ መንግሥት አዘዘ ፣ የኢየሩሳሌም ባለሥልጣኖች ግን ጉዳዩ አስቀድሞ በሚገባ የተመረመረ ስለሆነ እንደገና አይነሣብን ሲሉ መለሱ ፤ በ፲፱፻፬ ዓ. ም. ደግሞ በኢየሩሳሌም በነበረው በኢጣልያ ቆንስል አማካይነት የአጼ ምኒልክ ጥያቄ ለኢየሩሴሌም ባለሥልጣኖች ቀረበ ፣ እንደገና ደግሞ በ፲፱፻፯ ዓ. ም. የቱርክ መንግሥት ጉዳዩን ኢንፎርማል በሆነ መንገድ እንሥቶት አገሩን የያዘው የእን ግሊዝ መንግሥት የጉዳዩ ሁናቴ በ፲፰፻፹፱ ዓ. ም. የነበረውን መልክ አለመለወጡን አስ ታወቀ ፣ ይኸም ማለት ከተከራካሪዎቹ ወገኖች አንደኛው ለሌላው የባለ ንብረትነት መ ብት የሚሰጠውን ሥራ እንዲፈጸም የማይፈቅዱለትና የትኛውም ወገን የባለ ንብረትነት ይዞታ እንዳይደክምበት ለማሳደሻ የሚያስፈልገውን ወጭ ለመክፈል የማይስማማ ነው ።

ገዳሙ በክርክሩ ምክንያት በለቤት እጥቶ ፈራርሶ ስለነበረ መታደስ አስፈላጊው በመሆኑ ማዘጋጃ ቤት በ፲፱፻፲፱ ዓ. ም. እና በ፲፱፻፳፯ ዓ. ም. አድሶት የእርሻ ክፍል መሥሪያ ቤት ደግሞ በ፲፱፻፳፫ ዓ. ም. ዛፎችን አስመልምሉአል ።

መንግሥቱ በክርክሩ ሊገባ በፈለገ ቍጥር ኢትዮጵያውያን የንብረታቸው ማስረጃ ዎች በኢትዮጵያ ይገኛሉ በማለት ማስረጃዎቹን ለማቅረብ ቀጠሮ ጠየቁ ፣ ስለዚህም በ፲፱፻፳ ዓ. ም. በአዲስ አበባ የነበረው የግርማዊ የእንግሊዝ ንጉሥ ዋና ቆንስል ምር መራ እንዲያደርግ ታዘዘ ።

የተባሉት የንብረት ማስረጃ ጽሑፎች በኢትዮጵያ በሚኖሩ የመስኩብ ተወላጅ በር ን ኒከላስ በተባሉ ሰው እጅ እንደነበረና እኒህም ሰው ማስረጃዎችን እጅግ ከፍ ባለዋጋ ለአጼ ምኒልክ ሊሸጡ እንደሞከሩ የሚገልጽ ኢንፎርመሽን ተገኘ ፤ እኒህን የመሰሉ ማስረጃዎች በኮንስታንቲኖፕል ለነበረው የግርማዊ የእንግሊዝ ዋና ቆንስል እንዲመ ረምሩ በ፲፱፻፳፩ ዓ. ም. ቀረበ ፣ በሌላም በኩል ደግሞ እኒህ ማስረጃዎች የኢየሩሳሌም የኦርቶዶክስ ሲኖድ አበል ለኮፕቶች ሸጡት የሚል ወሬ በአገሩ ውስጥ ተዛመተ። የሆነ ሆኖ በለሙሉ ሥልጣን እንደራሴ ልዑል አልጋ ወራሽ ራስ ተፈሪ ስለ ንብረቱ ማስረጃ የተዛመተውን አሉ በልታ ምንም ያህል በለማመናቸው ተንኰሉ ያገኘው ደገፋ ያንኑ ያህል ትንሽ ነበር ።

በአሮጌው ከተማ ካላቸው ገዳም በስተቀር ከግንቡ ውጭ ቆንጆ ቤተ ክርስቲያን የሚገኝበት አንድ ገዳምና በከተማውም ውስጥ ባለብዙ ዋጋ የሆነ ንብረት ስለ አላቸው ዛሬ የኢትዮጵያውያን ሁናቴ በጣም ተሻሽሏል ።

በ፲፱፻፷፬ ዓ. ም. ልዑል ራስ ተፈሪ ኢየሩሳሌምን ሲጎበኙ በክርስቶስ መቃብር አዋሳኝ ከሚገኘው ከቅዱስ አብርሃም ገዳም ሥር ያለውን የምድርቤት ከኦርቶዶክሳዊው ፓትርያርክ በወርቅና በኢትዮጵያም ሊሰጡት በተስማሙት ንብረት ለውጥ እንዲ ሰጣቸው አደረጉ፤ይህም መለዋወጥ በመሃይምን ኦርቶዶክሳዊ ክበብና በቅዱስ ሲኖድያ የከረረ ክርክር አስነሣ፡ ይህ የምድር ቤት የተገዛበት ምክንያት ምድር ቤቱ በከፊል በዴር ኤል ሡልጣን ገዳም ሥር ስለሚገኝ ከኦርቶዶክስ ገዳም የሚያወርደውን ደረጃ ዘግቶ ከዴር ኤል ሡልጣን ወደ ምድር ቤቱ የሚያወርድ ደረጃ ለመሥራት ስለ ተፈለገ ነው፡ በመንግሥቱ የተደረገው መገበያየት የይርጋውን አዋጅ የሼር አድርጎ በመመል ከት የተደረገው መለዋወጥ ሊጸድቅ አለመቻሉን ለብፁዕነታቸው በመግለጽ ይኸው ሐሳብ ለልዑልነታቸው እንዲነገር ጠየቀ፡ ብፁዕነታቸውም የተጠየቁትን በልዑልነታ ቸው ሐኪም አማካይነት እንደፈጸሙ ለመንግሥቱ አስታወቁ።

ጥያቄውን የመደገፍ ለመከናተ ቅዱሳት ከሚሲዮኖች የሚያገለግል የከፕቶች ፓትር ያርክ አንድ ፓምፍሌት አሳትሟል፡ ዴሼን የሚባል ደራሲ በ፲፱፻፷፮ ዓ. ም. "ኢትዮጵ ውያንና መከነ ቅዱሳት" በሚባል አርእስት በጻፈው መጽሐፍ የኢትዮጵያውያን አስተያ የት ተጽፏል፡ ኢትዮጵያውያን በዝቅተኛው የቅዱስ ሚከኤል መቅደስ እንዲጸልዩ ተፈቅዶ አያውቅም ።

ስለዚህ በዓል አከባበር ሉቃስ ከ፷፯-፷፱ ገጽ ተመልከት

ይኸውም ሊሆን የቻለው ኢትዮጵያውያን "ራሃያ" ባለመሆናቸውና ምን ጊዜም ሊሆን የቱርክንና የግብጽን ገዢነት ባለመቀበላቸው ሊሆን ይችላል ።

የቀበሌው ገዢ በ፱ የካቲት ፲፱፻፷፭ ዓ. ም. በቍጥር ፵፬፻፷-፩ ለኢየሩሳሌም ከንቲባ የጻፉትንና ለከፕቶችና ለኢትዮጵያውያን የመነኮሳት አለቆች ያስተላለፉትን ደብዳቤ ተመልከት ።

በታላቁ ዱክ አሌክሳንደር የተመራው የመስኮብ ሚስዮን ከዋናዎቹ ወገኖች አን ድ ነበር፡ የንብረት ማስረጃዎቹን በማስታከክ ስለ ጣና ሐይቅና ስለ አልኮል ኮንሴሲዮን ንግግር ተጀምሮ ነበር፡ በ፲፬ እና በ፷፫ መስከረም የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር የጻፈውን ቍጥር-ኤ ምሥጢር ደብዳቤ ተመልከት ።

የካቲት ፳፩ ቀን ፲፱፻፶፱ ዓ. ም.
የመንገድ ቍጥር ፶፬

ለብፁዕ አቡነ ባስልዮስ
ሊቀ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ ፥

ብፁዕ ሆይ ፤

በኢየሩሳሌም ፥ በኢትዮጵያውያንና በኮፕቶች መካከል ስላለው የዴር ሡልጣን ገዳም ክርክር ፥ ከጥንቱም ይበልጥ ዛሬ በጣም እንደ ተካረረ ሆኗል ፥ ምክንያቱም በሕግ ረገድ አላገባብ ኮፕቶች ይጠቀሙበት የነበረውን የገዳሙን ይዞታ መብት አስለቀቀና ቸው ፥ የኛ መነከሳት ሰፈር የሆነ ሁሉ በጆርዳን መንግሥት ፍርድ መሠረት ስለ መታ ደሉ ነው ።

አሁንም ፥ እኛ በተሰጠን ብይን ክርክራችንን በመቀጠል ኮፕቶችም መብታችንን ለቀ ቅን ሲሉ የእስታቲስኮን ሕግ በመጥቀስ በሁለታችን መካከል ስላለው ትግል ፥ የጆርዳን መንግሥት በምኒስትሮች ኮሚሲዮን ነገሩ እንዲታይ ወሰና ፥ እኛ ነገረ ፈጅ ወልደን ችሎቱን በመጠበቅ ላይ ስለ ምንገኝ ፥ ያገሩ ጉዳይ ያለ ገንዘብ ኃይል ፍጻሜ አያገኝምና ብፁዕ አባታችን ስለዚሁ ነገር መከላከያ ከሁን ቀደም በ፵፰ ዓ. ም. በፈቀዱልኝ መሠ ረት የገንዘብ እርዳታ ያዙልኝ ዘንድ እለምናሁ ።

ብፁዕ ሆይ ፤

ግብጾችን እንዴት እንደ ተነሡብን ይረዱት ዘንድ ፥ በዓረብኛ የጻፉትን የጋዜጣ ትርጉም ከዚህ አያይዤ አቀርባለሁ ።

አባ ፊልጶስ ።

ኮፒ፡ ለግርማዊ ጃንሆይ ።

## የኮፕቶች ጋዜጣ ትርጉም

## የመጅሊስ አል ሚሊን ውሳኔ ማረጋገጥ ።

ከጥቅምት ወር ፲፱፻፶፯ እስከ ነሐሴ ወር ፲፱፻፶፯ ዓ. ም. በመጅሊስ አል ሚሊ ቀጥሎ በሚገኘው አርእስት የተወሰነ ነው ፣ ውሳኔ ራብጠት ኤል ቅዱስ ተመልክቷል ።

### በኢየሩሳሌም የሚገኘው የቅብጦች ጵጵስና ግቢ ፤

መጅሊሱ በኢየሩሳሌም ኩርሲ ስለሚገኙት ቅብጦች ማሰቡና መጠንቀቁ አልቀረም ። ይህ አብዛኛውን የሆነው ጳጳሱ ከሞተ ወዲህ ነው ። እንደዚሁም የኤኮኖሚ እኳኋን በጥፋት ላይ ሆኖ እዳው አስር ሺ ፓውንድ በመድረሱ አስቦበታል ፣ ስለ ዴር ሡልጣን የሚፈጠረውን ጥል ጠቅላላው የሕዝብ ሐሳብ ማስደንገጡ አልቀረም ። ይህ ነገር በጥንቃቄ ሊጠና እንደሚገባውና ወደ እውነቱ እንዲቃና ያስፈልጋል ። በ፳፯ ፣ ፲ ፣ ፶፯ ዓ. ም. መጅሊሱ ከአንድ ጳጳስ ጋር ለዚሁ ጉዳይ መልከተኞችን ለሥራ ላከ ። መልክተኛውም ሄዶ የጳጳሱን ግቢ ሥራ አኳኋን አጠና ። በዮርዳኖስ መንግሥት ውስጥ የሚገኘውን የቅብጦችን ቦታ ሁሉ ጐበኘ ። በዚህም ጊዜ ምንም የዓመት ገቢዋ ስምንት ሺ ፓውንድ ቢሆንም በችግር ላይ እየወደቀች መሄድዋን ተገንዝቧል ። ይህም መልክተኛ ስለ ኢየሩሳሌም ሀገረ ስብከት አስፈላጊውን ጥናትና ውሳኔ አድርጓል ። ይህም ጥናት የቅብጦችን ማኅበራዊ ኑሮና ጠበቂ እንዳስፈለጋቸው አስገንዝቧል። እንዲሁም በመንፈስ የሚጠነከሩብትንና የሚያድጉበትን ሥራ አድርጓል ።

እንደዚሁም በተደረገው ጥናት በቅብጦች መብት ላይ የሚደረገው ግፍ ከእውነት ጋር ተስማሚ አይደለም ። እስታቱስኮ የሚባለው ሕግ አኳኋን በደንበኛውና በእውነቱ የተከበረና የተጠበቀ ነው ።

ለዚህ ውሳኔ ራብጠት አል ቅዱስ የምታርገው መልስ፣ ራብጠት አል ቅዱስ ምንም በቅብጦች ፍቅርና በቅዱስ ማርቆስ ሀገረ ስብከት ያላት ፍቅር ከፍ ያለ ቢሆን ፣ ነፃነቷን የሚነክ ውሸት ፣ ትግሏን የሚያቃልል ፣ ድካሟን የሚደመስስ ውሸት በዚህ ውሳኔ በትመለከት ልትቃወም በልሞከረች ነበር ። አሁን ራብጠት አል ቅዱስ የዚህን ውሳኔ መሳሳት ለመንካት አእምሮ በሚቀበለው አድርጋ ይህንን ቀጥሎ የተመለከተውን ትጽፋለች ።

<u>አንደኛ</u> ፣ በመጅሊስ ሚሊ ወኪል እንዲህ የሚል ውሳኔ ወጣ ፤ በዴር ሡልጣን ንብረት ጉዳይ የመጣው ጥል ጠቅላላውን የሕዝብ ሐሳብ አስደንግጧል ። ይህም ማለት በቅብጦች ንብረት በሚሆን የዴር ሡልጣንን ማለት ነው ። እንዲህ ራብጠት አል ቅዱስ በብዙ ዘመን ውስጥ ሕግ የሚመሰክርላቸውን ንብረት ማደስ ቅብጦች መሆን እንደሚገባቸው ለመከራከር ትነሣለች ። እንግዶቻችን ሐበሾች በውስጣችን ሲኖሩ እኛን አስተናጋጆቻቸውን ትተው ለማደስ ፣ ግድግዳንና መስኮትን ለመቀበት የጆርዳንን መንግሥት ቢለምኑ ልመናቸውን ተቀብሎ ሥራው በ፲፱፻፶፯ ዓ. ም. በመስከረም ወር ተጀምሮ እየተስፋፋ ሄደ ። መስኮቶች እየበዙ ሄደው ወደ ስልሳ ደርሰዋል ፤ ፳-፴ የነበረው ፣

፴-፵ና ፵-፶ ሁናል ። እንደዚሁም ፶፩-፸፰ የሚሆን አዲስ መስኮት ተከፍቷል ፣ የዮርዳኖስም መንግሥት አኳኋኑን አስለክቶ ለማደሻ ፻፹፩ ፓውንድ አዋፍቷል ።

፶፩-፸፰ የወጣውን መስኮት የወጣበትን እንዲት ኢትዮጵያዊት ልዕልት ትኖርበታለች ፣ እንደዚሁም አዳዲስ የበርና የመስኮት ዕንጨቶች ተበጅተው በአንድ ዓይነት ቀለም ተቀብተዋል ፣ ከዋቂቶች በቀር አብዛኛው አሁን ታድሶ ይገኛል ። አሁን ከባለ ቤቶች ይልቅ የእንግዶች መኖሪያ ቤቶች ታድሰው ይታያሉ ፣ ይህም የሆነው የመነከሳት ኤጲስቆጶስ በሚሆኑት በአቡነ ፊልጶስ እስታቱስኮን በመተላለፍ ነው ።

አሁን ድምፃችንን የምናሰማው የመጅሊስ መቅደስ እንዲሁም በጳጳሳትና በኤጲስ ቆጶሳት የተወሰነ ውሳኔ ብፁዕ የሐበሻው ጳጳስ ፣ ኤጲስ ቆጶሳትን በሀገራቸው በሐበሻ ብቻ እንዲሾሙ እንጂ በሌላው እንዳይሾሙ ሕግን በማስታወስ ነው ። እንዲሁም ፴፭ኛውን የሐዋርያትን ሕግ በመጥቀስ ነው ። እርሱም ይህ ነው፣ ኤጲስ ቆጶስ በሀገረ ስብከቱ በስተቀ፤ ከዚያ ውጭ ሊሾሙ አይገባም ፣ ይህንን ግን ከአስፈላጊው ጠብቆ ፈቃድ ሳይወስድ ያደረገ እንደሆነ እርሱና ተሿሚው ይለዩ (ይወገዙ) ። ስለዚህ ፓትርያርኩ ለብፁዕ የሐበሻ ጳጳስ ወደ ውጭ እንዲሾም ያለ መጅሊሱ ፈቃድ አይሆንም ። እንግዲህ አስፈላጊው የኢየሩሳሌም አዛዥ የቀብጡ ጳጳስ መሆኑ ነው ። ራብጠት አል ቅዱስ በጽሑፍ መጅሊስ መቅደስን በ፲፱፻፵፫ ዓ. ም. ቢጠየቅ የስብሰባው ጸሐፊ እውነትም ይህ ነገር እንግዳ ነው ፣ ሆኖም ለወደፊት አይለመድም ሲል መልስ ሰጠ ። ይህም የሆነው የሐበሻው ጳጳስ ለገዳሙና ለመነከሳቱ የሚሆነውን ኤጲስ ቆጶስ ለመሾም ስለጠየቀ ነው እንጂ ጠባቂ ኤጲስ ቆጶስ አይደለም አለ ፣ ይኸውም የቤተ ክርስቲያን ሕግ እንደሚያዘው በፓትርያርክ ፈቃድ ጳጳስ ኤጲስ ቆጶስን ሲሾም ፣ ኤጲስ ቆጶሱ ዲያቆናትን ብቻ እንጂ ከህናት ሊሾም ሥልጣን የለውም ።

በጣም አስደናቂው አቡነ ፊልጶስ በጋዜጣ የሐበሾች ጳጳስ ብለው ስለ ራሳቸው ማውጣታቸው ነው ። እንደዚሁም በሐበሾች ገዳም በራፍ ላይ የሐበሾች ፓትርያርክ ግቢ ብለውጽፈዋል ፣ ይህም ልታይ በማለት ከቅድስና መራቅ ነው ።

ሁለተኛ ፣ የራብጠት አል ቅዱስ አባሎች ከሊባኖስ ወደ ካይሮ በሚመለሱበት ጊዜ በሐበሾች ገዳም ውስጥ ትልቅ ግንብ መገንባቱን ተረድተው ለመጅሊሱ ይህንኑ ለማመልከት ወደ ፓትርያርኬቱ ሄደው ነበር ። ይህንንም በመስከረም ፳፫ ፣ ፲፱፻፶፮ ዓ.ም. ሊያቀርቡ በሄዱበት ጊዜ ሦስት የሐበሾች መነከሳት በበትረካናው አርፈው ነበር ። በዚህም ጊዜ ፣ በኢየሩሳሌም ስለሚደረገው አባ ብንያምን ጠየቃቸው ። እነርሱም በእውነተኛነት አሥር መስኮቶች አስፍተን ፳፭ የነበረውን ፶ አድርገነዋል ሲሉ መሰከሩ ። ይህም የሆነው ቆሞስ ዳውድና ቆሞስ ሸኖዳ በፓትርያርኩ ግቢ በተገኙበት ጊዜ ነው ።

ሦስተኛ፣ የፓትርያርኩ መጅሊስ ይህንን ከተባሉት መነኮሳት ከተረዳ በኋላ፣ይህ በእስታቱስኮና በቅብጦች ገንዘብ ላይ መተላለፍ እንደሆነ አውቆ በነገሩ ተጠንቅቆ ለአማን መንግሥት፣ ለአገር ግዛት ሚኒስቴር፣ ለውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ለአገረ ገዥውና እንዲሁም ለክቡር የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ይህንን መተላለፍ አስታወቀ። ለነዚህ ለተባሉት ራብጠት አል ቅዱስ ደብዳቤን ጻፈች ። እንደዚሁ የፓትርኬቱ መጅሊስ በአማን ለሚገኘው የግብጽ አም

ባሳደርና ለአገረ ገዥው ቀጥሎ ያለውን ጻፈ፥ "አሁን በመጨረሻው ረግቶ በነበረው ይህ ንን ገዳም በመገንበት ብዙ ለውጥ ተደረገ፥ ይኸውም የክፍሎችን መስኮቶች በማስፋ ትና በሌላም ለውጭ የእስታቱስኮን ሕግ ተቃውሚል ።

<u>አራተኛ</u>፥ ይህ ደብዳቤ በኢየሩሳሌምና በአማን ደርሶ በነበረበት ጊዜ አቡነ ማርቆስ አል አንጦኒ ለፖሊስ ክስ አቅርበው ሦስት አዲስ መስኮቶች በመከፈታቸው አስረዳ ።

<u>አምስተኛ</u>፥ በአማን ያለው የግብጽ አምባሳደር ለከይሮ ፓትርያርኬት እንዲህ ሲል ጻፈ "የሥራ ክፍል ሠራተኛ በዴር ሡልጣን መስኮቶችና ሌሎችን ክፍሎች ማ ደስ ጀምሯል ። አባ እንጦንዮስም ሐበሾች መስኮትን እንዳስፋፉ አይቶ ይህንኑ ለማዘ ጋጃ ቤት በቴሌፎን አስታውቋል" ።

<u>ስድስተኛ</u>፥ መጅሊስ ሚሊ እንደራሴዎች ወደ ኢየሩሳሌም ላከ፤ ይህም እንደራሴ በደረሰ ጊዜ የማዘጋጃ ቤት ሹምንና ቅዱስ ቦታውን ተጠባባቂውን ተገናኛቸው ። በዚ ህም ጊዜ ይህ እንደራሴ ስለ ቅብጦች መብት ተከራክሮ እስታቱስኮ እንዳልተፈጸመና እንዳልተሠራበት ነገረ ። ከዚህ በኋላ ወደ ከይሮ ተመልሶ ከጸጸሳቱ ይህ ጽሑፍ ተላከ፥ "በተሠራው ሥራ ሁሉ እስታቱስኮ እንዳልተሠራበት በጠቅላላው እናመለክታለን። እስ ታቱስኮ ምንም ለውጥ ወይም ማደስ እንዳይደረግ ይከለክላል ። አሁንም ነገሩ እንዲጠ ብቅና እንዳለ እንዲሆን እንጠይቃለን" ።

<u>ሰባተኛ</u>፤ አባ እንጦንዮስ የመንግሥቱን መሐንዲስ የረዳውን ዳውድ የሚባለውን ሰው በተላኩት ወኪሎች ፊት አቅርቦ የመስኮቶቹ መለዋወጥና አሮጌዎች መቃጠላቸ ውን አስመሰከረ ።

## <u>የ በ ዓ ል  ወ ሬ ።</u>

፩ በ፳፭-፱-፶፯ ዓ. ም. የጋዛና የኢየሩሌም ጳጳስ የሆኑት አቡነ ዮሐንስ በትምህርት መጀመርያ ቀን ለመገናኘት ወደ ኢየሩሳሌም ሂደዋል ። እንደዚሁም የቅብ ጦች መሬት በሚሆነው በዴር ሡልጣን ሜዳ ላይ ሐበሾች የብፁዕነታቸውን ፈቃድ ጠይቀው የመስቀል በዓልን በሚያሳዩበት ጊዜ ፈቅደው በዓሉን ይመለ ከታሉ ።

፪ የጋዛና የኢየሩሳሌም ጳጳስ ብጹዕ አቡነ ዮሐንስ፥ ዴር ሡልጣን እንዲታደስ ፻፳፫ ፓውንድ ያወጣቸውን የዮርዳኖስን መንግሥት ለመክፈል ጠይቀዋል ። እስከሁን መንግሥቱ ለዚሁ መልስ አልሰጠም ። ጳጳሱም ይህ ገንዘብ በሕግ እን ዲከፈል ለማድረግ ይፋጠናሉ ።

<u>ጋዜጣን</u>፥ "የቅብጥ ኦርቶዶክስ ራብጠት አል ቅዱስ" ።

ኃምሳ ሁለተኛው ቍጥር
እ. ኤ. አ. ፲፱፻፶፯ ዓ. ም. ጥቅምት፥
ሙሉጌታ መልከ ጼዴቅ ።

## የሥራ መግለጫ ራፖ'ር ፣

### ለብፁዕ ወቅዱስ ፓትርያርክ ወርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ አበታችን አቡነ ባስልዮስ ፤

ብፁዕ ወቅዱስ ሆይ ፤

የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ከግብጾች ጋር ያላት መንፈሳዊ ግኑኝነት እጅግ የጐዳት (ያጠቃት) መሆኑ ግልጽ ነው ፣ ምክንያቱም በመላ ኢትዮጵያ መንፈሳዊ መብትን የግላቸው አድርገው ይዘው ፣ በራሷ ሥልጣን እንዳታስተምር አድርገው ጨቍነው ዛሬ እንሆ አገራችን ኢትዮጵያ በአእላፍ ሚሲዮንና በእስላም ተከባ ትገኛለች ፤ ስለሆነ ግን ይህን ሰፊውን አስተያየት ለብፁዕነትዎ ትቼ በኢየሩሳሌም በቅዱሳት መካናት በሚገኘው በኢትዮጵያ ማኅበራችን ላይም የግብጾች አጥቂነትና ተጋፊነት ከጥንት ጀምሮ እስከ አሁን ጊዜያችንም ግፉ እንደቀጠለ መኖሩን አስረዳለሁ ።

፩ - ዴር ሥልጣን የሚባለው ገዳም ከጎልጎታ ቤተ ክርስቲያን ተያይዞ በምሥራቃዊ ክፍል የሚገኘው ገዳም ዛሬ የኮፕቶች ንብረት ሆኖ እስከሚታየው ስፍራ ሳይቀር በመላው የኢትዮጵያ ርስት እንደነበረ ማስረጃው ይነግረናል ፣ ነገር ግን ፣ ኮፕቶች አሁን እነሱ ያሉበትን የዴር ሡልጣን ክፍል ተደላድለው እጅ ከደረጉ በኋላም ፣ ዛሬ ከኛው እጅ ያልወጣውንም ከዴር ሥልጣን አንድ ክፍል የሆነውን ገዳማችንን የኮፕቶች ርስት ነው ፣ በውስጡ ስፍራው የሚገኙት የሐበሻ መነኩሳትም እኛው በእንግድነት ተቀብለን ያስቀመጥናቸው እንግዶቻችን ናቸው ይላሉ ።

እንደዚህ ለማለት የረዳቸው ከላይ በመነሻው እንደገለጽኩት የኢትዮጵያን መንፈሳዊ ሥልጣን በመውሰዳቸው ምክንያት የኢትዮጵያ መነኩሳት ወደ ዳኛ በቀረቡ ቍጥር እነዚህ የኛ ጥገኞች ናቸው ፣ እንኳንስ በዚህ በውጭ አገርና በገራቸውም የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን በመላዋ የምትተዳደር በኛ በኮፕቶች ሥልጣን ሥር ነው ። ለነዚህም አሳዳሪያቸው እኛ ነን እያሉ ነገራቸው እንዳይደመጥ አድርገው ኢትዮጵያውንን ጨቍነው በርስታችን ሠልጥነውበት የኖሩት ስለዚህ ነው ።

፪ - ይህንን የኢትዮጵያውያንን ገዳም በኢትዮጵያዊ ጳጳስ ሥልጣን ሥር እንዲተዳደር ሆኖ በልዑል እግዚአብሔር ፈቃድ በግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ መልክም አስተ ያየት በቅዱስነትዎ ሸዋሚነት እኔ ተልኬ ኢየሩሳሌም ከገባሁበት ጊዜ ጀምሮም ኮፕቶች ይኸው አሮጌ ልማዳቸውን በመቀጠል በገንዘብ፣ በተንኮል ሥራ፣ ጋዜጣን በመጻፍ፣ የምሥርን መንግሥት ድጋፍ በማድረግ፣ ይኸውና በልዩ ልዩ አኳኋን ባለ ኃይላቸው እውነቱን በሐሰት ለማሸነፍ ሲታገሉ ይገኛሉ ።

ይሁን እንጅ በ፲፱፻፵፰ ዓ. ም. ብፁዕነትዎ ለቅዱስ ማርቆስ ቤተ ክርስቲያን ቡራኬ ከይሮ በተገኙበት ጊዜ በእስክንድርያ ፓትርያርክ በብፁዕ አቡነ ዮሳብ ፈቃድ በኢትዮጵያና በግብጾች መካከል ያለውን የዴር ሥልጣንን ገዳም ክርክር በስምምነት ለመጨረስ ታስቦ በተደረገው ኮሚስዮን መካከል የኮፕቶች ጳጳስ የነበረው አባ ያዕቆብ በኢትዮጵያውያን ላይ የተናገረውን የንቀትና የተግዳሮት ንግግር ፣ በማግሥቱም ኮፕቶች በዓ

ረብ ጋዜጣ የጸፉብንን ክብርን የሚነካ አስቀያሚ ቃል ከሰሙ በኋላ ብፁዕነትዎ ከእንግ ዲህ ወዲህ ለዚህ ነገር ምንም ብታደርግ በከፕቶች በኩል ቅርታ የለኝም ፡ እግዚአብ ሔር ይርዳህ ሲሉ መርቀው ለዚህ ሥራ መከላከያ ይሁንህ ብለው ልዩ ወጭ ከላኩልኝ በኋላ የተፈጸመውን የሥራውን ፍሬ እንደሚከተለው እዘረዝራለሁ ።

፩ኛ ፡ ከፕቶች ከላይ እንደተነገረው በበላይነት ሥልጣን የገዳማችንን መብት ይዘ ው ቤቶቹ ቢፈርሱ እንዳይጠገኑ ፡ ዝናም ቢያፈሱ እንዳይታደሱ ፡ ቢቄሽሹ እንዳይጸዱ አድርገው የማይደሱ መብት የኛ ነው ፡ ማንም አይገበበትም እያሉ ከልክለው የቤቶቹን መፍረስና የገዳሙም ቆሻሽነትና አስቀያሚነት ለተመልካች ሁሉ አስቀይሞ የነበረውን ለማሳደስ እንድንችል ።

፪ኛ ፡ ለትንሣኤና ለመስቀል ዓበይት በዓላት በምናከብርበት መላው ዓለም የኢት ዮጵያን ስነ በዓል ለመመልከት በሚሰበሰብበት ጊዜም፡ የግብጹ ጳጳስ ርስቱ መብቱ የኔ ነው ፡ እኔን ለምነው ካልሆነ በስተቀር በሩም አልከፍትም እያለ በዓላችንን ሰው እንዳ ይመለከተው በደምብ እንዳይከበር በዓሉ ይታጐል የነበረውን ለግብጹ ጳጳስ በኛ ላይ ይህን ያህል መብት የለውም፡ በሩም በጥንታዊው ሕግ በደምብ ይከፈታል እንጂ ኢት ዮጵያ መብት የሌለው ግብጹን በለመብት አድርጋ የግብጹን ጳጳስ ክፈትልን ብለን መለ መን የለብንም ብዬ ጠበቃ ገዝቼ በሕግ መሠረት ለጆርዳን መንግሥት ማመልከቻ አቅ ርቤ እውነተኛ ፍርድ ጠይቀን የጆርዳን መንግሥትም ያቀረብነውን ማመልከቻና የከፕ ቶችን መልስ መርምሮ ከተረዳ በኋላ ፡

ሀ ) የነዚህ የሁለቱ ጠበኞች የኢትዮጵያና ግብጾች ክርክር በፍርድ አልቆ በለመ ብት እስኪወሰን ድረስ ገዳሙን መንግሥት ያድሰዋል እንጂ ይህ ነገር በፍርድ ከማለቁ በፊት ሁለቱም ወገኖች ገዳሙን ለማደስ መብት የላቸውም ፡ መንግሥት ገዳሙን በማ ደስና በማጽዳት የሰውን ሕይወት ይጠብቃል ።

ለ ) ኢትዮጵያውያን የተለመደውን የመስቀልና የትንሣኤን በዓላት በሌሊት ሲያከ ብሩ በሩ በሕግ ይከፈትላቸዋል እንጂ ከፕቶችን መጠየቅ (ክፈቱልን ብሎ መለመን) የለባቸውም ።

ሐ ) ኢትዮጵያን ከጥንት ሲያያዝ የቆየውን የሃይማኖት አገልግሎታቸውን ማንም ሳይቃወማቸው መፈጸም ይችላሉ ሲል በኮሚስዮን ወስኖ ለሁለታችን ጠበኞች የሰጠ ንን መልክምና ትክክለኛው ብያኔውን በፎቶግራፍ አስነሥቼ ለቅዱስነትዎ ከሁን ቀደ ም የላኩት ማስረጃ በመዝገብ ቤትዎ ይገኛል ።

መ ) በዚህ ብያኔ መሠረት የጆርዳን መንግሥት የሥራ ሚኒስቴሩን አዝዞ በጣም ተበላሽቶና ወድቆ የነበረው ገዳማችንን የጥንት ሥራውን ሳይለቅ የድንጋይ ሥራ የነበ ረውን አዲስ ጥርብ ድንጋይ እያገባ በሲሚንቶ ሥራ የነበረውን፡ አዲስ ሲሚንቶ አሸዋ እያገባ ፡ በዕንጨትና በቆርቆሮ የነበረውን አዲስ ዕንጨትና አዲስ ቆርቆሮ እየገዛ አግ ብቶ ደህና አድርጎ ሠርቶታል ።

ሠ ) የገዳሙም ምድረ ግቢ እንደሚያውቁት የድንጋይ ጐራንጕርና የቆሻሻ መጣያ የነበረውን ምድረ ግቢውን፡ በሙሉ በሲሚንቶና በጠጠር ቤቱን አንጥፎ መንገዱንም ሁሉ በደምብ ሠርተው ግቢው ሁሉ የአስፋልት መንገድ መስሎ ተሠርቶ ይገኛል፡ በዴ ር አብርሃምና በመስከቦች መካከል ወደ ገዳማችን በኩል ተንጠልጥሎ ድንጋይ እየወ ደቀ ሰውነታችንን ያሰጋ የነበረው የጥንቱን አሮጌውን ግንብ ፡ በሲሚንቶ አድርገው በሚገባ ተሠርቶ ይገኛል ።

ረ) የሚበቃ ብርሃን የሚሰጥ መስኮት ያልነበራቸውንም ቤቶች፣ ጠባብ የነበረውን እያሰፉ፣ ያልነበረውም መስኮት አዲስ እያወጣ በደምብ ሆኖ ተሠርቶ ይገኛል ።

ይኸውም ሥራ ከፕቶችን አለመጠን አስቀይሟቸው ከኛ መኖሪያ የእንግዶቻችን መኖሪያ የበለጠ ሆኖ ተሠራ በማለት ያቀረቡት አቤቱታና በኛ ገዳም የተፈጸመውን የሥራ ዝርዝር በመግለጽ የግብጹን ሕዝበ ክርስቲያን በመላው በኛ ላይ ለማስነሣት የጻፉት ጋዜጣ ባማርኛ አስተርጕሜ ብፁዕነትዎ ይመለከቱልኝ ዘንድና ወደፊትም ግብጾች ያላረፉልን መሆናቸውን በመግለጽ፣ የካቲት ፳፩ ቀን ፲፱፻፶፱ ዓ. ም. በቁጥር ፶፬ ማመልከቻና አባሪ አድርጌ የላክሁት የጋዜጣው ግልባጭ በመዝገብ ቤትዎ የሚገኝ መሆኑን በማስረዳት ይመለከቱልኝ ዘንድ አሁንም አሳስባለሁ፤ የከፕቶቹ ጋዜጣ እኔን ሾመው በመላክዎ ምክንያት አድርጎ የብፁዕነትዎንም ክብር ይነካል ።

ብፁዕ ወቅዱስ ፓትርያርክ ሆይ፤

ይህ ሁሉ የሥራ ዝርዝር ሊፈጸም የተቻለው ሥራብት ያውልህ ብለው በሰጡኝ ገንዘብ ኃይል መሆኑን እገልጻለሁ ።

ብፁዕ ወቅዱስ አባታችን ሆይ፤

ከዚህ በላይ በቅድስናዎ እርዳታ የተፈጸመውን ገለጽሁ እንጂ፣ ነገሩ በዚህ ብቻ የተወሰነ አይደለም ። ከፕቶች እስታቱስኮ የተባለውን ሕግ ተላልፈው ከሕጉ ውሳኔ በኋላ የገዳማችንን መክፈቻ ወስደው ሁለቱን ቤተ ክርስቲያኖቻችን አርባዕቱ እንስሳና ቅዱስ ሚከኤልን ከጥንት ጀምሮ የሃይማኖት አገልግሎት እንፈጽምባቸው የነበረውን ያለ ፍርድ በራሳቸው ሥልጣን ብቻ በግፍ ዘግተውብን ስለሚገኙ፣ ይህ ተግባር ከሕግ ውጭ በግፍ የተሠራብን ነውና፣ በዓለም መንግሥታት ታውቆ ከተወሰነው ሕግ (ከእስታቱስኮ) በኋላ ሕጉን ተላልፈው ከፕቶች የወሰዱብን የገዳማችን መክፈቻ ለኛ ለባለቤቶቹ ይመለሳል ። በግፍ የተዘጉ ቤተ ክርስቲያኖቻችንም ለኛ ለባለ ንብረቶች ተለቀው እንድንቀድስባቸው ሆነው ከፕቶችም ይህን ቅዱስን መቅደስ መመላለሻ ጕዳና ከማድረግ እንዲከለከሉ ይፈረድባቸዋል ። ስንል፣ አዲስ ክስ አቅርበን፣ ቅን ፍርድን በመጠባበቅ እንገኛለን ።

ይህም ሲሆን፣ ያለንን ማስረጃ ሁሉ ሰብስበን ከነ ክልሼው ጭምር አዘጋጅተን በዓረብኛና በእንግሊዝኛ አጽፈን ለተሰጠን ፈራጅ ያቀረብነው መጽሐፍ ለማዘጋጀት የተቻለው በላይኛው መሥመር በተገለጸው ብፁዕነትዎ በሰጡኝ ገንዘብ ኃይል እርዳታ መሆኑን አስረዳለሁ ።

ብፁዕ ወቅዱስ ፓትርያርክ አባታችን ሆይ፣

ወደ ፊትም በጸሎትዎ ይፈጸምልናል ብለን የቀጠልነው የከፕቶች ተጋድሎ እንሱም በጻፉት ጋዜጣ እንደገለጹት፣ እንደዚሁ በቀላል የሚያልቅ አለመሆኑን ግልጽ ነውና፣ የተለመደው እርዳታዎንና ጸሎትዎን ሳያቋርጡ እስከ ፍጻሜው ያረዱን ዘንድ በማሳሰብ ንግግሬን አቆማለሁ ።

ዕድሜ ለግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ፤
ዕድሜ ለቅድስናዎ፤

ታዛዥዎ አባ ፊልጶስ ።

ከፍተው ኢትዮጵያውያኖችን በተጠቀሱት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ውስጥ የሃይማኖት አገልግሎታቸውን እንዳይፈጽሙ ቢከለክሏቸውም ኢትዮጵያውያኖቹ ወደ ቅዱስ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን አደባባይ በሚያስኬደው ወደ ምዕራብ በሚከፈተው በር በኩል ሬሳቸውን ያለ እንዳች ክርክር ተሸክመው ምን ጊዜም ሲያልፉ መኖራቸውን እመሰክራለሁ ።

የመስከሬው ፊርማ
ያዕቆብ ኢብራሂም ቃዑድ
የራማላህ ተወላጅ ።

እኔ የራማላህ ዓቃቤ ሕግ ያዕቆብ ኢብራሂም ቃዑድ የተባለው የራማላህ ተወላጅ እፊቴ ቀርቦ ዛሬ ሚያዝያ ፯ ቀን ፲፱፻፶፬ ዓ. ም. ምስክርነቱን የሰጠና የፈረመ መሆኑን አረጋግጣለሁ ።

ፊርማ ዓብደላ ማክሱድ ኤል ኼሪ
የራማላህ ዓቃቤ ሕግ ።

የራማላህ ፍ/ቤት ማኅተም

የጆርዳን መንግሥት ሐሽማይት ያገር ግዛት ሚኒስቴር
<u>የኢየሩሳሌም አውራጃ ከሚሽነር ጽሕፈት ቤት</u>

ቀጥር ፓ. M/8/49 (3) 154

18 / ሐምሌ / 53

ብፁዕ ኢትዮጵያዊ ጳጳስ
ኢየሩሳሌም

ግንቦት ፲፰ ቀን ፲፱፻፶፫ የተጻፈ ደብዳቤዎን ጠቅሼ በቅድስት እሌኒ ቤተ ክርስቲያን (ሡልጣን ገዳም) የሚገኘው ግምብ ለርስዎ የሚገባ መሆኑን ሊገልጡና ሊያስታውቁ የተናገሩት ፣ እንዲሁም የዚሁን ባለ ቤትነት ማረጋገጫና ማሳመኛ እንዲሆን በማለት ወደ አገር ግዛት ምክትል ምኒስትርና የኢየሩሳሌም አውራጃ ከሚሽነር አባላቱ (ሙታሳሪፍ) የተባሉት ፣ በርስዎ ማኅበርና በግብጥ ማኅበር መከከል ፣ የዚሁ ገዳም ባለቤትን ለማግኘት የተነሣውን ክርክር ለመመርመር ወደቆመው ከሚስዮን ያቀረቡትን ጽሑፍ እያስታወስኩ ክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር የከሚሲኑን ራፖርር ከመረመሩ በኋላ በውስጡ ያለውን አደራነት እንድትቀበሉት ለብፁዕነትዎ አስታውቃለሁ ።

፩. በ፲፱፻፳፬ ዓ. ም. ስለ ቅድስት ሀገር የወጣው ትእዛዝ እንደሚወስነው ፣ ደምበኛ ከሚስዮን እስኪቋቋም ድረስ ጉዳዩ እንዳለ እንዲቆይ ፣ ይህም ማለት ግብጦች ያደርጉት እንደነበረ በመስቀልና በፋሲካ በዓላቶች ጊዜ በስተ ግራ የሚገኘውን ግራ በር እየፈቱ እንዲቆዩ ኢትዮጵያውያኖች ደግሞ ሌላውን ፈቃድ ሳይጠይቁ እቤተ ክርስቲያኑ ገብተው ሥርዓታቸውን እንዲፈጽሙ ፣ በገዳሙም ውስጥ እንደፈቱ እንዲያገለግሉ ስለምን ግብጦች ሊከለክሏቸው መብት የላቸውም ።

፪. በገዳሙ ሊታደስ የሚያስፈልግ ነገር እንዳለ በማናቸውም ጊዜ ሁለቱም ወገኖች ያልተስማሙ እንደሆነ መንግሥት ይፈጽመዋል። እንግዲያውስ ጉዳዩ እላይ ባለው ሁኔታ እንደ ተበየነ እንዳለ ሆኖ ይቈይ ተብሏልና እንዲያውቁትና እንዲያከብሩት ተስፋ አለኝ ።

አክባሪዎ
(ሐሰን ኤል ካቲብ)
የኢየሩሳሌም አውራጃ ከሚሽዮነር ።

አ ባ   ፊ ል ጶ ስ
የኢትዮጵያ ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ጳጳስ ፣
የፖስታ ሣጥን ቍጥር ፹፮ — የስልክ ቍጥር ፫፻፵፫
ኢ የ ሩ ሳ ሌ ም ።

ኢየሩሳሌም የካቲት ፳፯ ቀን ፲፱፻፶፱ ዓ. ም.

ለክቡር
የኢየሩሳሌምና የመካነ ቅዱስ አገረ ገዢ
ኢየሩሳሌም
ጆርዳን ።

ክቡር ሆይ ፣

አስቀድሜ ለክቡርነትዎ የማክበር ሰላምታዬን ሳቀርብ ፣ ከዚህ ቀጥሎ የተዘረዘሩት ሁናቴዎች በኢትዮጵያውያኖችና በኮፕቶች መካከል ያለውን ክርክር ቅዳሜ የካቲት ፳፫ ቀን ፲፱፻፶፱ ዓ. ም. ለሚያይ ኮሚሲዮን ክቡርነትዎ እንዲያቀርብልኝ ተስፋ አደርጋለሁ።

በ፲፱፻፫ ዓ. ም. አፄ ምኒልክ አንድ የኢትዮጵያ ዴሌጋሲዮን በደጃዝማች መሸሻ መሪነት ወደ ኢየሩሳሌም ልከው ነበር ፣ ይህ ዴሌጋሲዮን የዴር ኤል ሱልጣን ገዳምና የቁልፎቹን ፣ እንዲሁም በአቅራቢያው የሚገኙትን የአርባዕቱ እንስሳ ቤተ ክርስቲያንና የቅዱስ ሚካኤል ቤተ ክርስቲያን ጉዳይ ለማጥናት ተልኮ ነበር ።

ኮሚሲዮኑ ሰፊ ጥናት ካደረገ በኋላ ፣ አያሌ ደብዳቤዎች በኢየሩሳሌም ለሚገኙት ልዩ ልዩ ባለሥልጣኖች ከጻፈ በኋላ ከዚህ ቀጥሎ ያለውን መልስ ለማግኘት ችለዋል ።

፩ የግሪክ ኦርቶዶክስ ፓትርያርክ ዳሚያኖስ የሰጡት መልስ ፣ ይህ መልስ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክሳውያኖች ቤተ ክርስቲያን መብት በሚል አርእስት በተጻፈው መጽሐፍ ውስጥ ሰነድ ቍጥር ፬ ላይ ተዘርዝሮ ይገኛል ፣ መልሱም ፣ —

ሀ) ከጥንት ጊዜ ጀምሮ የኢትዮጵያ መነኮሳት በዴር ኤል ሱልጣን ገዳም ውስጥ ነዋሪዎች ነበሩ ፣

ለ) በፓትርያርኩ እጅ የሚገኙት የሱልጣን ትእዛዞች በተለይም በ፲፪፻፴፮ እና በ፲፪፻፴፬ ዓ. ም. ውስጥ በኮፕቶችና በኢትዮጵያውያኖች መካከል በተነሣው ጠብ ምክንያት የተሰጠው ትእዛዝ የዴር ኤል ሱልጣን ገዳም የኢትዮጵያውያኖች ርስት መሆኑን በግልጽ ያስረዳል ፤

ሐ) ሆኖም ኮፕቶች የገዳሙን ቊልፍ የዛሬ ፶፱ ዓመት የወሰዱበትን አኳኋን ለማወቅ አልተቻለም ፤

መ) ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ጠቡ ሳያቋርጥ በሁለቱም ወገኖች መካከል ቀጥሎአል ፤

ሠ) ይህ በመሆኑ ምክንያት ኢትዮጵያውያኖች በነገሩ ውስጥ ባሉት ቤተ ክር ስቲያኖች ውስጥ የቤተ ክርስቲያንን ስነ ሥርዓት ለመፈጸም ሳይችሉ ቀርተዋል ይላል ።

፱ የአርመኖች ኦርቶዶክስ ፓትርያርክ አርቲን የሰጡት መልስ፣ ይህ መልስ የኢትዮ ጵያ ኦርቶዶክሳውያን ቤተ ክርስቲያን መብት በሚል አርእስት በተጻፈው መጽሐፍ ውስጥ ሰነድ ቍጥር ፰ ላይ ተዘርዝሮ ይገኛል፣ መልሱም፣ —

ሀ) ከጥንት ጊዜ ጀምሮ የኢትዮጵያ መነኮሳት በዴር ኤል ሱልጣን ገዳም ውስጥ ነዋሪዎች ናቸው፤

ለ) ኮፕቶች የገዳሙን ቍልፍ የዛሬ ፵ ዓመት የወሰዱበት አኳኋን ለማወቅ አልተቻለም፤

ሐ) ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ጠቡ ሳያቋርጥ በሁለቱም ወገኖች መካከል ቀጥሎአል፣

መ) ይህ በመሆኑ ምክንያት በተባሉት ቤተ ክርስቲያኖች ውስጥ ከቅርብ ዓመታት ጊዜ ጀምሮ የቤተ ክርስቲያን ስነ ሥርዓት ከመፈጸም አቋርጠ ዋል፣ ይላል ።

፲ የሶሪያውያኖች ጳጳስ ኤልያስ የሰጡት መልስ፣ ይህ መልስ፣ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክሳ ውያኖች ቤተ ክርስቲያን መብት በሚል አርእስት በተጻፈው መጽሐፍ ውስጥ ሰነድ ቍጥር ፳ ላይ ተዘርዝሮ ይገኛል፣ መልሱም፣ —

ሀ) ከጥንት ጊዜ ጀምሮ የኢትዮጵያ መነኮሳት በተባለው ገዳም ውስጥ ነዋሪ ዎች ናቸው፤

ለ) ኮፕቶች የገዳሙን ቁልፍ የወሰዱበትን አኳኋን ለማወቅ አልተቻለም፤

ሐ) ኢትዮጵያውያኖቹ የቤተ ክርስቲያንን ስነ ሥርዓት በአቅራቢያዎቹ ቤተ ክርስቲያኖች የሚፈጽሙም ቢሆን፣ በጠቡ ምክንያት ስነ ሥርዓቱን ከመ ፈጸም አቋርጠዋል ።

፲፩ የማሮናይት ፓትርያርክ ቫይካር ኤል ሙዓለም የሰጡት መልስ፣ ይህ መልስ፣ ከዚህ በላ ይ በተጠቀሰው መጽሐፍ በሰነድ ቍጥር ፲ ላይ ተዘርዝሮ ይገኛል፣ መልሱም፣ —

ሀ) በእጃቸው በሚገኝ ሰነድ ሁሉ እንደሚታየው ዴር ኤል ሱልጣን የኢት ዮጵያውያኖች ንብረት ነው፤

ለ) በኢየሩሳሌም በኖርኩበት በ፲፩ ዓመት ጊዜ ውስጥ የኢትዮጵያ መነኮ ሳት ሁሉ ጊዜ በተባለው ገዳም ውስጥ ሲኖሩ አይቶናል፤

ሐ) ከዚህም በቀር የኢትዮጵያ መነኮሳት በአርባዕቱ እንስሳና በቅዱስ ሚካ ኤል ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ሥርዓተ ቅዳሴ ሲፈጽሙ ራሴ ተካፋይ ሆኛ ለሁ፣ ይላል ።

፲፪ የአርመን ካቶሊክ ፓትርያርክ ቫይካር የኦኪም ቱማያን የሰጡት መልስ፣ በሰነድ ቍጥር ፱ ላይ ተዘርዝሮ ይታያል፣ መልሱም፣ —

ክፍተው ኢትዮጵያውያኖችን በተጠቀሱት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ውስጥ የሃይማኖት አገልግሎታቸውን እንዳይፈጽሙ ቢከለክሏቸውም ኢትዮጵያውያኖቹ ወደ ቅዱስ መቃብሩ ቤተ ክርስቲያን አደባባይ በሚያስኬደው ወደ ምዕራብ በሚከፈተው በር በኩል ሬሳቸውን ያለ አንዳች ክርክር ተሸክመው ምን ጊዜም ሲያልፉ መኖራቸውን እመሰክራለሁ ።

የመሰከረው ፊርማ
ያዕቆብ ኢብራሂም ቃውድ
የራማላህ ተወላጅ ።

እኔ የራማላህ ዓቃቤ ሕግ ያዕቆብ ኢብራሂም ቃውድ የተባለው የራማላህ ተወላጅ እፊቴ ቀርቦ ዛሬ ሚያዝያ ፯ቀን ፲፱፻፶፩ ዓ. ም. ምስክርነቱን የሰጠና የፈረመ መሆኑን አረጋግጣለሁ ።

ፊርማ ዓብደላ ማክሱድ ኤል ኬሪ
የራማላህ ዓቃቤ ሕግ ።

የራማላህ ፍ/ቤት ማኅተም

የጆርዳን መንግሥት ሐሽማይት ያገር ግዛት ሚኒስቴር

የኢየሩሳሌም አውራጃ ኮሚሽነር ጽሕፈት ቤት

ቀጥር ፓ. M/8/49 (3) 154

18 / ሐምሌ / 53

ብፁዕ ኢትዮጵያዊ ጳጳስ
ኢየሩሳሌም

ግንቦት ፲፮ ቀን ፲፱፻፶፫ የተጻፈ ደብዳቤዎን ጠቅሼ በቅድስት እሌኒ ቤተ ክርስቲያን (ሡልጣን ገዳም) የሚገኘው ግምብ ለርስዎ የሚገባ መሆኑን ሊገልጡና ሊያስታውቁ የተናገሩት ፤ እንዲሁም የዚሁን ባለ ቤትነት ማረጋገጫና ማሳመኛ እንዲሆን በማለት ወደ አገር ግዛት ምክትል ምኒስትርና የኢየሩሳሌም አውራጃ ኮሚሽነር አባላቱ (ሙታሳሪፍ) የተባሉት ፤ በርስዎ ማኅበርና በግብጥ ማኅበር መከከል ፤ የዚሁ ገዳም ባለቤትን ለማግኘት የተነሣውን ክርክር ለመመርመር ወደቆመው ኮሚስዮን ያቀረቡትን ጽሑፍ እያስታወስኩ ክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር የኮሚሲኑን ራፖር ከመረመሩ በኋላ በውስጡ ያለውን አደራነት እንድትቀበሉት ለብፁዕነትዎ አስታውቃለሁ ።

፩. በ፲፱፻፳፱ ዓ. ም. ስለ ቅድስት ሀገር የወጣው ትእዛዝ እንደሚወስነው ፤ ደምበኛ ኮሚስዮን እስኪቋቋም ድረስ ጕዳዩ እንዳለ እንዲቆይ ፤ ይህም ማለት ግብጦች ያደርጉት እንደነበረ በመስቀልና በፋሲካ በዓላቶች ጊዜ በስተ ግራ የሚገኘውን ግራ በር እየፈቱ እንዲቆዩ ኢትዮጵያውያኖች ደግሞ ሌላውን ፈቃድ ሳይጠይቁ እቤተ ክርስቲያኑ ገብተው ሥርዓታቸውን እንዲፈጽሙ ፤ በገዳሙም ውስጥ እንደፊቱ እንዲያገለግሉ ስለምን ግብጦች ሊከለክሏቸው መብት የላቸውም ።

፪. በገዳሙ ሊታደስ የሚያስፈልግ ነገር እንዳለ በማናቸውም ጊዜ ሁለቱም ወገኖች ያልተስማሙ እንደሆነ መንግሥት ይፈጽመዋል። እንግዲያውስ ጕዳዩ አላይ ባለው ሁኔታ እንደ ተበየነ እንዳለ ሆኖ ይቈይ ተብሏልና እንዲያውቁትና እንዲያከብሩት ተስፋ አለኝ ።

አክባሪዎ

(ሐሰን ኤል ካቲብ)

የኢየሩሳሌም አውራጃ ኮሚሽዮነር ።

አባ ፊልጶስ
የኢትዮጵያ ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ጳጳስ ፥
የፖስታ ሣጥን ቍጥር ፳፫ — የስልክ ቍጥር ፫፪፻፵፯
ኢ የ ሩ ሳ ሌ ም ።

ኢየሩሳሌም የካቲት ፳፯ ቀን ፲፱፻፶፱ ዓ. ም.

ለክቡር
የኢየሩሳሌምና የመካነ ቅዱስ አገረ ገዢ
ኢየሩሳሌም
ጆርዳን ።

ክቡር ሆይ ፥

አስቀድሜ ለክቡርነትዎ የማክበር ሰላምታዬን ሳቀርብ ፥ ከዚህ ቀጥሎ የተዘረዘሩት ሁናቴዎች በኢትዮጵያውያኖችና በኮፕቶች መካከል ያለውን ክርክር ቀዳሚ የካቲት ፳፫ ቀን ፲፱፻፶፱ ዓ. ም. ለሚያይ ኮሚሲዮን ክቡርነትዎ እንዲያቀርቡልኝ ተስፋ አደርጋለሁ።

በ፲፱፻፫ ዓ. ም. አፄ ምኒልክ አንድ የኢትዮጵያ ዴሌጋሲዮን በደጃዝማች መሸሻ መሪነት ወደ ኢየሩሳሌም ልከው ነበር ፥ ይህ ዴሌጋሲዮን የዴር ኤል ሱልጣን ገዳምና የቁልፎቹን ፥ እንዲሁም በአቅራቢያው የሚገኙትን የአርባዕቱ እንስሳ ቤተ ክርስቲያንና የቅዱስ ሚካኤል ቤተ ክርስቲያን ጉዳይ ለማጥናት ተልኮ ነበር ።

ከሚሲዮኑ ሰፊ ጥናት ከደረገ በኋላ ፥ አያሌ ደብዳቤዎች በኢየሩሳሌም ለሚገኙት ልዩ ልዩ ባለሥልጣኖች ከጻፈ በኋላ ከዚህ ቀጥሎ ያለውን መልስ ለማግኘት ችለዋል ።

፩ የግሪክ ኦርቶዶክስ ፓትርያርክ ዳሚያኖስ የሰጡት መልስ ፥ ይህ መልስ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክሳውያኖች ቤተ ክርስቲያን መብት በሚል አርእስት በተጻፈው መጽሐፍ ውስጥ ሰነድ ቍጥር ፬ ላይ ተዘርዝሮ ይገኛል ፥ መልሱም ፥ —

ሀ) ከጥንት ጊዜ ጀምሮ የኢትዮጵያ መነኮሳት በዴር ኤል ሱልጣን ገዳም ውስጥ ነዋሪዎች ነበሩ ፣

ለ) በፓትርያርኩ እጅ የሚገኙት የሱልጣን ትእዛዞች በተለይም በ፲፯፻፳፮ እና በ፲፯፻፳፱ ዓ. ም. ውስጥ በኮፕቶችና በኢትዮጵያውያኖች መካከል በተነሣው ጠብ ምክንያት የተሰጠው ትእዛዝ የዴር ኤል ሱልጣን ገዳም የኢትዮጵያውያኖች ርስት መሆኑን በግልጽ ያስረዳል ፤

ሐ) ሆኖም ኮፕቶች የገዳሙን ቁልፍ የዛሬ ፺፱ ዓመት የወሰዱበትን አኳኋን ለማወቅ አልተቻለም ፤

መ) ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ጠቡ ሳያቋርጥ በሁለቱም ወገኖች መካከል ቀጥሎአል ፤

ሠ) ይህ በመሆኑ ምክንያት ኢትዮጵያውያኖች በነገሩ ውስጥ ባሉት ቤተ ክር ስቲያኖች ውስጥ የቤተ ክርስቲያንን ስነ ሥርዓት ለመፈጸም ሳይችሉ ቀርተዋል ይላል ።

፱ የአርመኖች ኦርቶዶክስ ፓትርያርክ አርቲን የሰጡት መልስ፣ ይህ መልስ የኢትዮ ጵያ ኦርቶዶክሳውያን ቤተ ክርስቲያን መብት በሚል አርእስት በተጻፈው መጽሐፍ ውስጥ ሰነድ ቍጥር ፳ ላይ ተዘርዝሮ ይገኛል ፣ መልሱም ፣ —

ሀ) ከጥንት ጊዜ ጀምሮ የኢትዮጵያ መነኩሳት በዴር ኤል ሱልጣን ገዳም ውስጥ ነዋሪዎች ናቸው ፤

ለ) ከፕቶች የገዳሙን ቍልፍ የዛሬ ፵ ዓመት የወሰዱበት አኳኋን ለማወቅ አልተቻለም ፤

ሐ) ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ጠቡ ሳያቋርጥ በሁለቱም ወገኖች መካከል ቀጥሎአል፣

መ) ይህ በመሆኑ ምክንያት በተባሉት ቤተ ክርስቲያኖች ውስጥ ከቅርብ ዓመታት ጊዜ ጀምሮ የቤተ ክርስቲያን ስነ ሥርዓት ከመፈጸም አቋርጠ ዋል ፣ ይላል ።

፲ የሰሪያውያኖች ጳጳስ ኤልያስ የሰጡት መልስ፣ ይህ መልስ፣ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክሳ ውያኖች ቤተ ክርስቲያን መብት በሚል አርእስት በተጻፈው መጽሐፍ ውስጥ ሰነድ ቍጥር ፳ ላይ ተዘርዝሮ ይገኛል ፣ መልሱም ፣ —

ሀ) ከጥንት ጊዜ ጀምሮ የኢትዮጵያ መነኩሳት በተባለው ገዳም ውስጥ ነዋሪ ዎች ናቸው ፤

ለ) ከፕቶች የገዳሙን ቁልፍ የወሰዱበትን አኳኋን ለማወቅ አልተቻለም ፤

ሐ) ኢትዮጵያውያኖቹ የቤተ ክርስቲያንን ስነ ሥርዓት በአቅራቢያዎቹ ቤተ ክርስቲያኖች የሚፈጽሙም ቢሆን፣ በጠቡ ምክንያት ስነ ሥርዓቱን ከመ ፈጸም አቋርጠዋል ።

፲፩ የማሮናይት ፓትርያርክ ቫይከር ኤል ሙዓለም የሰጡት መልስ፣ ይህ መልስ፣ ከዚህ በላ ይ በተጠቀሰው መጽሐፍ በሰነድ ቍጥር ፯ ላይ ተዘርዝሮ ይገኛል ፣ መልሱም ፣ —

ሀ) በእጃቸው በሚገኝ ሰነድ ሁሉ እንደሚታየው ዴር ኤል ሱልጣን የኢት ዮጵያውያኖች ንብረት ነው ፤

ለ) በኢየሩሳሌም በኖርኩበት በ፲፭ ዓመት ጊዜ ውስጥ የኢትዮጵያ መነኩ ሳት ሁለ ጊዜ በተባለው ገዳም ውስጥ ሲኖሩ አይቶኛል ፤

ሐ) ከዚህም በቀር የኢትዮጵያ መነኩሳት በአርበዕቱ እንስሳና በቅዱስ ሚካ ኤል ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ሥርዓተ ቅዳሴ ሲፈጽሙ ራሴ ተካፋይ ሆኛ ለሁ ፣ ይላል ።

፲፪ የአርመን ካቶሊክ ፓትርያርክ ቫይከር የአኪም ቱማያን የሰጡት መልስ ፣ በሰነድ ቍጥር ፱ ላይ ተዘርዝሮ ይታያል ፣ መልሱም ፣ —

ሀ) በኢየሩሳሌም ፴፰ ዓመት ጊዜ ስኖር የኢትዮጵያ መነኮሳት በዴር ሡልጣን ገዳም ውስጥ ሲኖሩ አይቻለሁ ፣ እንዲሁም የተባሉት መነኮሳት በአርባዕቱ እንስሳ ቤተ ክርስቲያንና በቅዱስ ሚካኤል ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ከ፹፰ ዓመት ጊዜ ጀምሮ እስከ ነሐሴ ፳፫ ቀን ፲፱፻፳ ዓ. ም. ድረስ የሃይማኖት አገልግሎታቸውን ሥርዓት ሲፈጽሙ አይቻለሁ ፣ ይላል ።

፯ የላቲን ፓትርያርክ ቫይካር ጀኔራል በኢየሩሳሌም የሰጡት መልስ ፣ በሰነድ ቁጥር ፯ ላይ ተዘርዝሮ ይገኛል ፣ መልሱም ፣ —

ሀ) የላቲን ሽማግሌዎች በሰጡት ምስክርነትና ራሴ ባገኘሁት መሠረት ፣ ዴር ሡልጣን የኢትዮጵያውያኖች ርስት ነው ፤

ለ) እንዲሁም የኢትዮጵያ መነኮሳት ከገዳሙ አቅራቢያ በሚገኙት ቤተ ክርስቲያኖች ውስጥ ሥርዓተ ቅዳሴ ይፈጽሙ ነበር ፣ ይላል ።

፰ የመካነ ቅዱስ ጠባቂ አባ ፊሊፖ ሬቼ ከዚህ በላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ፣ ሰነድ ቁጥር ፲ ላይ የሰጡት መልስ ፣ —

ሀ) በኢየሩሳሌም ከ፹፬ ዓመት ጊዜ ጀምሮ በዚሁ ሥራ ስሠራ ነበር ፤

ለ) የፍራንሲስካን መነኮሳት በዚሁ ጊዜ ውስጥ ከ፲፮ኛው የመስቀል ጉዞ ቦታ ወደ ቅዱስ መቃብር ሚዳ በሚወስደው በር ሲተላለፉ አይቻለሁ ፤

ሐ) የደቡባዊውን በር ቍልፍ በዚያን ጊዜ በኢትዮጵያውያን መነኮሳት እጅ ይገኝ ነበር ይላል ።

፱ ፍራንሲስ እስጤፋን በመጽሐፉ ሰነድ ቍጥር ፲፭ ላይ የሰጡት መልስ ፣ —

ሀ) ይህንኑ የምስክርነት ቃል ስሰጥ ዕድሜዬ ፹፩ ዓመት ነው ፤

ለ) ክፕቶች በተስቦ በሽታ ምክንያት የኢትዮጵያ መነኮሳት ሁሉ ካለቁ በኋላ የዴር ሡልጣን ቍልፍ በእጃቸው አግብተዋል ፤

ሐ) ኢብራሂም ፓሻ (ማለት በዚያን ጊዜ የግብጽ ገዢ የነበረው) ኮፕቶች ቍልፉን እንዲይዙ ረድተዋቸዋል ፤

መ) ኢብራሂም ፓሻ ከሞተ በኋላ አንዳንድ ኢትዮጵያውያኖች ወደ ኢየሩሳሌም መጥተው ገዳማቸውን መልሰው በእጃቸው ያለክርክር ለማግባት ቻሉ፤

ሠ) አንድ ኮፕት መነኵሴ በሞተ ጊዜ ኮፕቶች በኢትዮጵያውያኖች ገዳም በኩል የቀብሩን ሥርዓት ለመፈጸም ለማለፍ ሲጠይቁ ኢትዮጵያውያኖቹ ይከለክሉዋቸው ነበር ፤

ረ) ይህ ሁናቴ እያሌ የኢየሩሳሌም ሽማግሌዎች የሚያውቁት ነው ፣ ይላል ።

፲ የግሪክ ኦርቶዶክሳውያን ሙኽታር በኢየሩሳሌም ጆርጆስ ዓጣ ኩታብ ፣ ማንሱር ሚኬልና ሐና ዘናኒሬ በተባለው መጽሐፍ ፣ ሰነድ ቍጥር ፲፱ ላይ የሰጡት መልስ ፣ —

ሀ) ዴር ሡልጣን የኢትዮጵያውያኖች ንብረት ነው ፤

ለ) ከገዳሙ አጠገብ የሚገኙት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች የኢትዮጵያውያኖች ንብረት ሆነው ኢትዮጵያውያኖቹም የቤተ ክርስቲያንን ስነ ሥርዓት ይፈጽሙበት ነበር ፣ ይላል ።

፲ በኢየሩሳሌም የሚገኙት አርመኖች ፣ በሰነድ ቍጥር ፲፫ ላይ የሰጡት መልስ ፣ —

ሀ) ዴር ኤል ሱልጣንና አጠገቡ የሚገኙት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች የኢትዮጵያ መነኮሳት ናቸው ይላል ።

፲፩ በኢየሩሳሌም የሚገኙት የላቲን ሰዎች፣በሰነድ ቍጥር ፲፬ ላይ የሰጡት ምስክርነት ፣ —

ሀ) ዴር ኤል ሱልጣንና አጠገቡ የሚገኙት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች የኢትዮጵያውያኖች ንብረት ናቸው ፤

ለ) የኢትዮጵያ መነኮሳት የቅዳሴ ስነ ሥርዓት በሁለቱ ቤተ ክርስቲያኖች ውስጥ ሁለ ጊዜ ይፈጽሙ ነበር ፣ ይላል ።

፲፪ ሽማግሌው ያቆብ ኢብራሂም ኤል ካውድ ፣ በሰነድ ቍጥር ፲፮ ላይ የሰጡት ምስክርነት ፣ —

ሀ) ይህንን ምስክርነት ስሰጥ ዕድሜዬ ፹፫ ዓመት ሆኖ ገና በሕይወቴ የምገኝ ሰው ነኝ ፤

ለ) እናቴ በዴር ኤል ሱልጣን ውስጥ ለኢትዮጵያውያን መነኮሳት ታገለግል ነበር ፤

ሐ) በሕይወቴ ጊዜ ውስጥ ክፕቶች የሰሚኑን በር በኃይል ሲከፍቱት አይቻለሁ ፣ ድሮ በሩ ትንሽ ቀዳዳ ብቻ ነበረው ፤

መ) ክፕቶቹ በስተሰሜኑ በር በላይኛው ክፍል አንድ የድንጋይ ጽሑፍ ካስቀመጡ በኋላ ፣ የግሪክ ፓትርያርክ ድንጋዩን እንዲያነሡ አዘዙዋቸው ፤

ሠ) ከገዳሙ አጠገብ በሚገኙት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ውስጥ የኢትዮጵያ መነኮሳት ሥርዓተ ቅዳሴ ሲፈጽሙ አይቻለሁ ፤

ረ) ኢትዮጵያውያኖቹ ወደ ቅዱስ መቃብር ቤተ ክርስቲያን በሚወስደው በገዳሙ ደቡብዊ በር በኩል ሙታውያኖቻቸውን ሲያሳልፉ አያቸው ነበርሁ ፣ ይላል ።

ከዚህ በላይ የተዘረዘሩት ማስረጃዎች ከዚህ ቀደም ካቀረብናቸው ማስታወሻዎች በተጨማሪነት የቀረቡ ናቸው ።

ስለዚህ ኢትዮጵያውያኖቹ ክቡር ከሚሲዮኑ ከዚህ ቀጥሎ የተዘረዘረውን ጉዳይ እንዲፈጽምላቸው በማክበር ያመለክታሉ ፣

፩ የዴር ኤል ሱልጣን ገዳምና አብረውት ያሉት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ንጉሣዊው ትእዛዝ በተሰጠበት ጊዜ በነበሩበት አኳኋን እንዲመለሱ ፣ የተባለው ንጉሣዊው ትእዛዝ በዚል ቂዕዳ ፣ ፲፪፻፶፱ ዓመተ ሂጂራ የተሰጠ ነው ። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ የተፈጸሙት ግፎችና አገባብ የሌላቸው ተግባሮች ሁሉ ሕገ ወጥ ተብለው እንዲቈጠሩ ፤

፪ ከፕቶች በ፲፱፻፷፰ እና በ፲፱፻፸ ዓመተ ምሕረት ውስጥ የፈጸሙዋቸው ሕገ ወጥ ተግባሮች ሁሉ ንጉሣዊውን ትእዛዝ ተቃዋሚዎች ተብለው እንዲቈጠሩ፥

፫ ዴር ኤል ሡልጣን ሁለ ጊዜ በኢትዮጵያ መነኩሳት እጅ የነበረና ርስታቸው መሆኑን ተገልጾ ቁልፎቹንም ለኢትዮጵያውያኖች ተመላሽ እንዲያደርጉ አንድ ውሳኔ እንዲሰጥ፤

፬ የተባሉት ሁለት ቤተ ክርስቲያኖች ቁልፎች እንደዚሁ ለኢትዮጵያ መነኩሳት ተመላሽ እንዲሆኑና እንዲሁም የቤተ ክርስቲያኖቹ መብት ከታወቀ በኋላ ማና ቸውም ሰው በተባለው ገዳም በኩል እንዳይተላለፍ የተከለከለ መሆኑን መወ ሰን፤

፭ ኢትዮጵያውያኖቹ በተባለው ገዳምና ቤተ ክርስቲያኖች ላይ ያላቸውን መብት እንዲታወቅላቸው ደጋግመው ሲጠይቁ በመኖራቸው ምክንያት ማናቸውም የይርጋ ሕግ ሊያግዳቸው የማይችል መሆኑን መወሰን፤

፮ ስለ ገዳማችን ውሳኔ የሚሰጥበት መሠረት የአማራይት ቃል ኪዳንና እንዲ ሁም የሡልጣን ሰሊምና የሡለይማን ትእዛዞች መሆናቸውን መወሰን።

ክቡር ኮሚሲዮኑ ጉዳዩን አብራርቶ ከተመለከተ በኋላ፥ተገቢ የሆነ ትክክለኛ ውሳኔ እንደሚሰጠን በመተማመን አስቀድመን ምስጋናችንንና የማክበር ሰላምታችንን በትሕ ትና እናቀርባለን።

ፍጹም አክባሪዎ፥
አባ ፊልጶስ
የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን
ጳጳስ በኢየሩሳሌም።

እስታቱስኮ፣ከሚባለው መስተር ክስት ከጻፈው መጽሐፍ የተቀዳ ከእንግሊዝ
ጳጳስ ዘንድ የመጣልኝ፣ ፲፱፻፶፰ ዓ-ም ጥቅምት ፲ ቀን
አባ ፊልጶስ ።

## የዴር ኤል ሡልጣን ገዳም ፣

የዴር ኤል ሡልጣን ገዳም ከጎልጎታ ቤተ ክርስቲያን ጋር በስተምሥራቅ የሚዋሰን ነው፤ይህ ገዳም በገረገራው መኻከል አንድ ጉልላትና=ዶም=የመነከሳት መኖሪያ የሆኑ ጐጆዎች ኖሮት በኩፕት ዘበኛ ይጠበቃል፣ ጉልላቱም የቅድስት እሌኒ መቅደስ መብራት ነው፣ ገዳሙ የሚገኘው በ፲፱፻፶፰ ዓ. ም. በክርስቲያኖች ወረራ ጊዜ በፈረሰው አሁንም የፍራሹ ምልክት በሚታይበት ጥንት የአውጉስጢን ቀሳውስት መዘዋወሪያ በነበረው ሥፍራ ላይ ነው፣ ወደ ጎልጎታ በሚወስደው መታላለፊያ በሩ የሚከፈተው የቅዱስ ሚክኤል መቅደስና የአርባዕቱ እንስሳ መቅደስ ከገዳሙ ጋር የተያያዙ ናቸው ።

ኮፕቶችና ኢትጵያውያን በየበኩላቸው ዴር ሡልጣን የሚባለው ገዳም የየራሳችን ነው ይላሉ፣ ኮፕቶች ግን በዚያ የሚገኙትን ኢትዮጵያውያን በእንግድነት እንደተቀበሏቸውና በእነሱ ፈቃድ ብቻ እንዲቀዩ እንጂ ባሰቤቶች እንዳይደሉ አድርገው ይናገራሉ፤ የክርክሩም ታሪክ በጣም ረጅምና የተሳሰረ ነው፣ የኢትዮጵያና የኮፕት ቤተ ክርስቲያን እምነት አንድ ሆኖ የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን የአሌክሳንድርያው የመንበረ ማርቆስ ልጅ ሆኖ ሁል ጊዜም የሚሾምላት ሊቀ ጳጳስ ከኮፕት ሊቃውንት መካከል በመሆኑ ይህ በሁለቱ መኻከል ያለው ክርክር በተለይ የሚያሳዝን ነው ።

እያሌ የመኻከለኛው መቶ ዘመናት ደራሴዎች የኮፕቶችና የኢትዮጵያውያኖች "የኖቢያ„ መነከሳት በጎልጎታ አካባቢ እንደነበሩ ሲመሰክሩ ኢትዮጵያውያን በመካን ቅዱሳት ከፍ ያለ መብት እንደነበራቸው ያረጋግጣሉ፣ በአሥራ አራተኛው መቶ ዓመት ትንሽዋ የግብፅ ቅድስት ማርያም መቅደስና ደግሞ በአሥራ እምስተኛው መቶ ዓመት በመዘዋወሪያው የሚገኘው የተድላ መቅደስ በኢትዮጵያውያን እጅ ነበረ፣በአሥራ ሰባተኛው መቶ ዓመት ግን እንደሌሎች ታናናሽ የክርስቲያን ኮሙኒቲዎች ሁሉ የቱርክን ገገር ግብር መክፈል ስለ እቃታቸው ቤተ ክርስቲያኑ ራሱ ተወሰደባቸው እነሱ እንደሚሉት እስከዛሬ በእጃቸው ያለውን የዴር ሡልጣንን ገዳም ብቻ ይዘዋል ።

ኮፕቶች ደግሞ በበኩላቸው ዴር ሡልጣን የተባለው ገዳም ምን ጊዜም የራሳቸው ንብረት እንደነበረና የሃይማኖት ጓደኞቻቸው የሆኑት ኢትዮጵያውያን ንብረታቸው ተወርሶ ማረፊያ ባጡ ጊዜ በርኅራኄ እንዳስጠጉአቸው ይናገራሉ ።

በእንደዚህ ያለው ሁናቴ በአርባዕቱ እንስሳ መቅደስ እንዲጸልዩ ተፈቅዶላቸው ስለ ገዳሙ የተነሣው ክርክር ለመጀመርያው ጊዜ ባለፈው መቶ ዓመት ተሰማ፣እስከዚህ ጊዜ ድረስ ፀንቶ የተቋቋመው ድርጅት እንደምን እንደተናጋና በመካናት ቅዱሳት ጉ

ዳይ እኒህ ሁለት እንትማማች ቤተ ክርስቲያናት የቅርብ ጎደኞች በመሆን ፈንታ በምን ምክንያት እንደተጣሉ በግልጽ አይታወቅም ፤ ኢትዮጵያውያን ከዴር ሡልጣን ገዳም በተባረሩ ጊዜ በጥቅምት ፲፯-፲፰፻፰ ዓ. ም. በቃዲው የተጻፈ የነበራቸውን ዝርዝር የሚያሳይ ጽሑፍ በኮፕቶች እጅ ይገኛል ፤ በዚሁ ጊዜ በመንግሥት ፈቃድ ገዳሙን እንዲያሳድሱ የሚያስረዱ አራት ወይም አምስት ጽሑፎች ለማቅረብ ይችላሉ ፣ ገዳሙን መያዛቸውን የሚጠቅስ ቀደም ብሎ የተጻፈ አንድ ጽሑፍ ደግሞ በእጃቸው ይገኛል ።

በ፲፰፻፴፰ ዓ. ም. እጅግ የሚያስፈራ ተስቦ በሽታ በኢየሩሳሌም ገብቶ ስለነበረ ኢትዮጵያውያን ሁሉ ብሙሉ አለቁ ይባላል ፤ ይኸውም የሆነው ኢብራሂም ፓሻ ኢየሩሳሌምን በያዘበት ጊዜ ስለሆነ ፣ የኢትዮጵያውያንን ጽሑፎችና ቤተ መጻሕፍት የንብረት ካርታቸውንም ጭምር ተላላፊ በሽታ ነክ አስመስለው በማቅረብ ለማቃጠል የፓሻውን ፈቃድ አግኝተው ኮፕቶች በዚህ አጋጣሚ ሳይጠቀሙበት የቀሩ አይመስልም ፤ ደግሞም የቤተ ክርስቲያናትንና የገዳሙን ቊልፍ መፍቻዎች እጃቸው ለማግባት ቻሉ ፣ የኒህ የሁለት ኮሚኒቲዮዎች ክርክር በአሥራ ዘጠነኛው መቶ ዓመት መላው ቢቀጥልም ኢትዮጵያውያን በ፲፰፻፷፫ ዓ. ም. የቊልፍ መፍቻውን እጃቸው ያገቡ ይመስላል ።

የቱርክ መንግሥት ምርመራ አድርጎ የሰጠው ብይን ኮፕቶችን የሚደግፍ ነበር ፣ ኢትዮጵያውያንም የቊልፍ መፍቻውን አንሰጥም በማለት እምቢ ስለአሉ ሌሎች ቊልፎች ተበጅተው መፍቻቸው ለኮፕቶች ተሰጠ ፣ ይኸውም የሆነው አጼ ቴዎድሮስ ከታላቂ ብሪታንያ ጋር ግጭት ባደረጉበት ጊዜ ስለነበረ ኢትዮጵያውያንን በደላቸው ።

ኮፕቶች የሰሜኑን በር እንዲያሰሩ ማዘጋጃ ቤት በ፲፰፻፹፱ ዓ. ም. ሲፈቅድላቸው ሁለተኛው ግጭት ተደረገ ፣ ኮፕቶች መላው የሰሜኑን ግድግዳ ለማፍረስ ፈልገው ነበር ፣ ነገር ግን በይርጋ ደምብ መሠረት የቱርክ መንግሥት ከለከላቸው ፣ ኢትዮጵያውያኖችም ኮፕቶች እንዳች መለዋወጥ ለማድረግ መብት የላቸውም ሲሉ በብርቱ ከመቃወማቸው ሌላ የኮፕቱን ሊቀ ጳጳስ ዘለፉዋቸው በዚህም ምክንያት ኢትዮጵያውያን ከጥንት ጀምሮ በአርባዕቱ እንስሳ መቅደስ ለመጸለይ የነበራቸውን መብት ኮፕቶች ከለከሏቸው ።

ጉዳዩ ለቱርክ መንግሥት ቀርቦ ስለ ነበረ መቅደሱን ለኢትዮጵያውያን እንዲከፍቱላቸው ኮፕቶች ሳያስገድዳቸው ቀረ ፣ ሆኖም ኢትዮጵያውያን ለራሳቸው ብቻ የሚያገለግል በር በገዳሙ በስተምሥራቅ ግድግዳ እንዲከፍቱ ፈቀደላቸው ፣ በዚህም ጊዜ ምንም እንኳን ኮፕቶች በብርቱ ቢቃወሙ ኢትዮጵያውያን የፋሲካን ጸሎታቸውን የሚያደርሱበት ድንኳን በገዳሙ ጣሪያ ላይ እንዲተክሉ ተፈቀደላቸው ።

ከዚህ አድላዊ ውሳኔ በኋላ ኢትዮጵያውያን ምንም ያህል ትግላቸውን ቢያጠነክሩ፣ የቱርክ መንግሥት በዚህ አስቸጋሪ ጉዳይ ኮፕቶችን በመደገፍ ስለ አዘነበለ ምንም ሊያደርጉ አልቻሉም ።

ከዚህም በስተቀር ኢትዮጵያውያን የሚጠይቁት ንብረት የራሳቸው መሆኑን የሚደግፍ ጽሑፍ ማስረጃ ሊያቀርቡ ከቶ አልቻሉም ።

የኢትዮጵያውያን ጽሑፍ ማስረጃዎች ሁሉ በ፲፰፻፴፰ ዓ. ም. እንደተቃጠሉ ከዚህ በላይ ተነግሯል ፣ ሆኖም እኒህ ማስረጃዎች በኢትዮጵያ ይገኛሉ የሚል ታሪክ እየገነነ ሄደ ፣ የማስረጃዎችም መኖርና አለመኖር የፈጠረው መጠራጠር የውጭ አገር መንግሥት በነገሩ እንዲገባ አጋጣሚ ጊዜ ሆነ ፣ መስኩብ በመካናት ቅዱሳት ያላትን ምኞት ለመዘርጋት ይህ አጋጣሚ ጊዜ ሆኖ ስለ አገኘችው ኢትዮጵያ እንዲመለስላት ከምትጠይቀው ንብረት በከፊል እንድታገኝ መገበባት ከተደረገ በኋላ የኢትዮጵያን ጥያቄ ደገፈች፤ ስለዚህም በ፲፰፻፺፫ ዓ. ም. በመስኩብ አምባሳደር ጠያቂነት የዴር ኤል ሡልጣን ገዳም ጉዳይ እንደገና እንዲመረመር የቱርክ መንግሥት አዘዘ ፣ የኢየሩሳሌም ባለሥልጣኖች ግን ጉዳዩ አስቀድሞ በሚገባ የተመረመረ ስለሆነ እንደገና አይነሣብን ሲሉ መለሱ፤ በ፲፱፻፬ ዓ. ም. ደግሞ በኢየሩሳሌም በነበረው በኢጣልያ ቆንስል አማካይነት የአጼ ምኒልክ ጥያቄ ለኢየሩሴሌም ባለሥልጣኖች ቀረበ ፣ እንደገና ደግሞ በ፲፱፻፯ ዓ. ም. የቱርክ መንግሥት ጉዳዩን ኢንፎርማል በሆነ መንገድ እንሥቶት አገሩን የያዘው የእንግሊዝ መንግሥት የጉዳዩ ሁናቴ በ፲፰፻፶፪ ዓ. ም. የነበረውን መልክ አለመለወጡን አስታወቀ ፣ ይኸም ማለት ከተከራካሪዎቹ ወገኖች አንደኛው ለሌላው የባለ ንብረትነት መብት የሚሰጠውን ሥራ እንዲፈጽም የማይፈቅዱለትና የትኛውም ወገን የባለ ንብረትነት ይዞታ እንዳይደክምበት ለማሳደሻ የሚያስፈልገውን ወጭ ለመክፈል የማይስማማ ነው ።

ገዳሙ በክርክሩ ምክንያት ባለቤት አጥቶ ፈራርሶ ስለነበረ መታደስ አስፈላጊው በመሆኑ ማዘጋጃ ቤት በ፲፱፻፲፱ ዓ. ም. እና በ፲፱፻፳፪ ዓ. ም. አድሶት የእርሻ ክፍል መሥሪያ ቤት ደግሞ በ፲፱፻፳፫ ዓ. ም. ዛፎችን አስመልምሎአል ።

መንግሥቱ በክርክሩ ሊገባ በፈለገ ቍጥር ኢትዮጵያውያን የንብረታቸው ማስረጃዎች በኢትዮጵያ ይገኛሉ በማለት ማስረጃዎቹን ለማቅረብ ቀጠሮ ጠየቁ ፣ ስለዚህም በ፲፱፻፳ ዓ. ም. በአዲስ አበባ የነበረው የግርማዊ የእንግሊዝ ንጉሥ ዋና ቆንስል ምርመራ እንዲያደርግ ታዘዘ ።

የተባሉት የንብረት ማስረጃ ጽሑፎች በኢትዮጵያ በሚኖሩ የመስኩብ ተወላጅ ባሮን ኒከላስ በተባሉ ሰው እጅ እንደነበረና እኒህም ሰው ማስረጃዎችን እጅግ ከፍ ባለዋጋ ለአጼ ምኒልክ ሊሸጡ እንደሞከሩ የሚገልጽ ኢንፎርመሽን ተገኘ፤ እኒህን የመሰሉ ማስረጃዎች በከንስታንቲኖፕል ለነበረው የግርማዊ የእንግሊዝ ዋና ቆንስል እንዲመረምሩ በ፲፱፻፳፩ ዓ. ም. ቀረበ ፣ በሌላም በኩል ደግሞ እኒህ ማስረጃዎች የኢየሩሳሌም የኦርቶዶክስ ሲኖድ አባል ለኮፕቶች ሸጡት የሚል ወሬ በአገሩ ውስጥ ተዛመተ። የሆነ ሆኖ ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴ ልዑል አልጋ ወራሽ ራስ ተፈሪ ስለ ንብረቱ ማስረጃ የተዛመተውን አሉ ባልታ ምንም ያህል በለማመናቸው ተንኰሉ ያገኘው ደገፉ ያንኑ ያህል ትንሽ ነበር ።

በአሮጌው ከተማ ካላቸው ገዳም በስተቀር ከግንቡ ውጭ ቆንጆ ቤተ ክርስቲያን የሚገኝበት አንድ ገዳምና በከተማውም ውስጥ ባለብዙ ዋጋ የሆነ ንብረት ስለ አላቸው ዛሬ የኢትዮጵያውያን ሁናቴ በጣም ተሻሽሏል ።

በ፲፱፻፷፪ ዓ. ም. ልዑል ራስ ተፈሪ ኢየሩሳሌምን ሲጐበኙ በክርስቶስ መቃብር አዋሳኝ ከሚገኘው ከቅዱስ አብርሃም ገዳም ሥር ያለውን የምድርቤት ከኦርቶዶክሳዊው ፓትርያርክ በወርቅና በኢትዮጵያም ሊሰጡት በተስማሙት ንብረት ለውጥ እንዲሰጣቸው አደረጉ፤ይህም መለዋወጥ በመሃይምን ኦርቶዶክሳዊ ክበብና በቅዱስ ሲኖዶያ የከረረ ክርክር አስነሣ፡ ይህ የምድር ቤት የተገዛበት ምክንያት ምድር ቤቱ በከፊል በዴር ኤል ሡልጣን ገዳም ሥር ስለሚገኝ ከኦርቶዶክስ ገዳም የሚያወርደውን ደረጃ ዘግቶ ከዴር ኤል ሡልጣን ወደ ምድር ቤቱ የሚያወርድ ደረጃ ለመሥራት ስለ ተፈለገ ነው፡ በመንግሥቱ የተደረገው መገበያየት የይርጋውን አዋጅ የሼር አድርጎ በመመልከት የተደረገው መለዋወጥ ሊጸድቅ አለመቻሉን ለብፁዕነታቸው በመግለጽ ይኸው ሐሳብ ለልዑልነታቸው እንዲነገር ጠየቀ፡ ብፁዕነታቸውም የተጠየቁትን በልዑልነታቸው ሐኪም አማካይነት እንደፈጸሙ ለመንግሥቱ አስታወቁ።

ጥያቄውን የመደገፍ ለመከናተ ቅዱሳት ከሚሲዮኖች የሚያገለግል የኮፕቶች ፓትርያርክ አንድ ፓምፍሌት አሳትሟል፡ ዱሼን የሚባል ደራሲ በ፲፱፻፷፮ ዓ. ም. "ኢትዮጵውያንና መከነ ቅዱሳት" በሚባል አርእስት በጻፈው መጽሐፍ የኢትዮጵያውያን አስተያየት ተጽፏል፡ ኢትዮጵያውያን በዝቅተኛው የቅዱስ ሚካኤል መቅደስ እንዲጸልዩ ተፈቅዶ አያውቅም ።

ስለዚህ በዓል አከባበር ሉቃስ ከ፷፯-፷፱ ገጽ ተመልከት

ይኸውም ሊሆን የቻለው ኢትዮጵያውያን "ራሃያ" ባለመሆናቸውና ምን ጊዜም ሊሆን የቱርክንና የግብጽን ገዢነት በለመቀበላቸው ሊሆን ይችላል ።

የቀበሌው ገዢ በ፱ የካቲት ፲፱፻፷፭ ዓ. ም. በቍጥር ፵፱፻፹-፭ ለኢየሩሳሌም ከንቲባ የጻፉትንና ለኮፕቶችና ለኢትዮጵያውያን የመነኮሳት አለቆች ያስተላለፉትን ደብዳቤ ተመልከት ።

በታላቁ ዱክ አሌክሳንደር የተመራው የመስኮብ ሚስዮን ከዋናዎቹ ወገኖች አንድ ነበር፡ የንብረት ማስረጃዎቹን በማስታከክ ስለ ጣና ሐይቅና ስለ አልኮል ኮንሴሲዮን ንግግር ተጀምሮ ነበር፡ በ፲፬ እና በ፳፫ መስከረም የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር የጻፈውን ቍጥር-ኤ ምሥጢር ደብዳቤ ተመልከት ።

የካቲት ፳፩ ቀን ፲፱፻፶ ዓ. ም.
የመንገድ ቍጥር ፶፬

ለብፁዕ አቡነ ባስልዮስ
ሊቀ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ ፤

ብፁዕ ሆይ ፤

በኢየሩሳሌም ፣ በኢትዮጵያውያንና በኮፕቶች መካከል ስላለው የዴር ሥልጣን ገዳም ክርክር ፤ ከጥንቱም ይበልጥ ዛሬ በጣም እንደ ተካረረ ሆኗል ፤ ምክንያቱም በሕግ ረገድ አላገባብ ኮፕቶች ይጠቀሙበት የነበረውን የገዳሙን ይዞታ መብት አስለቀቀናቸው ፤ የኛ መነከሳት ሰፈር የሆነ ሁሉ በጆርዳን መንግሥት ፍርድ መሠረት ስለ መታደሉ ነው ።

አሁንም ፤ እኛ በተሰጠን ብይን ክርክራችንን በመቀጠል ኮፕቶችም መብታችንን ለቀቅን ሲሉ የአስታቲስኮን ሕግ በመጥቀስ በሁለታችን መካከል ስላለው ትግል ፤ የጆርዳን መንግሥት በምኒስትሮች ኮሚሲዮን ነገሩ እንዲታይ ወሰና ፤ እኛ ነገረ ፈጅ ወልደን ችሎቱን በመጠበቅ ላይ ስለ ምንገኝ ፤ ያገሩ ጉዳይ ያለ ገንዘብ ኃይል ፍጻሜ አያገኝምና ብፁዕ አባታችን ስለዚሁ ነገር መከላከያ ከሁን ቀደም በ፵፩ ዓ. ም. በፈቀዱልኝ መሠረት የገንዘብ እርዳታ ያዙልኝ ዘንድ እለምናሁ ።

ብፁዕ ሆይ ፤

ግብጾችን እንዴት እንደ ተነሡብን ይረዱት ዘንድ ፤ በዓረብኛ የጻፉትን የጋዜጣ ትርጕም ከዚህ አያይዤ አቀርባለሁ ።

አባ ፊልጶስ ።

ክፍ፡ ለግርማዊ ጃንሆይ ።

## የኮፕቶች ጋዜጣ ትርጉም
## የመጅሊስ አል ሚሊን ውሳኔ ማረጋገጥ ።

ከጥቅምት ወር ፲፱፻፶፯ እስከ ነሐሴ ወር ፲፱፻፶፯ ዓ. ም. በመጅሊስ አል ሚሊ ቀጥሎ በሚገኘው አርእስት የተወሰነ ነው ፣ ውሳኔ ራብጠት ኤል ቅዱስ ተመልክቷል ።

## በኢየሩሳሌም የሚገኘው የቅብጦች ጵጵስና ግቢ ፤

መጅሊሱ በኢየሩሳሌም ኩርሲ ስለሚገኙት ቅብጦች ማሰቡና መጠንቀቁ አልቀረም ። ይህ አብዛኛውን የሆነው ጳጳሱ ከሞተ ወዲህ ነው ። እንደዚሁም የኤኮኖሚ እኳኋን በጥፋት ላይ ሆኖ እዳው አስር ሺ ፓውንድ በመድረሱ አስቦበታል ፣ ስለ ዴር ሡልጣን የሚፈጠረውን ጥል ጠቅላላው የሕዝብ ሐሳብ ማስደንገጡ አልቀረም ። ይህ ነገር በጥንቃቄ ሊጠና እንደሚገባውና ወደ እውነቱ እንዲቃና ያስፈልጋል ። በ፳፮ ፣ ፲ ፣ ፶፯ ዓ. ም. መጅሊሱ ከአንድ ጳጳስ ጋር ለዚሁ ጉዳይ መልክተኞችን ለሥራ ላከ ። መልክተኛውም ሄዶ የጳጳሱን ግቢ ሥራ አኳኋን አጠና ። በዮርዳኖስ መንግሥት ውስጥ የሚገኘውን የቅብጦችን ቦታ ሁሉ ጐበኘ ። በዚህም ጊዜ ምንም የዓመት ገቢዋ ስምንት ሺ ፓውንድ ቢሆንም በችግር ላይ እየወደቀች መሄድዋን ተገንዝቧል ። ይህም መልክተኛ ስለ ኢየሩሳሌም ሀገረ ስብከት አስፈላጊውን ጥናትና ውሳኔ አድርጓል ። ይህም ጥናት የቅብጦችን ማኅበራዊ ኑሮና ጠበቂ እንዳስፈለጋቸው አስገንዝቧል። እንዲሁም በመንፈስ የሚጠነክሩበትንና የሚያድጉበትን ሥራ አድርጓል ።

እንደዚሁም በተደረገው ጥናት በቅብጦች መብት ላይ የሚደረገው ግፍ ከእውነት ጋር ተስማሚ አይደለም ። እስታቱስኮ የሚባለው ሕግ አኳኋን በደንበኛውና በእውነቱ የተከበረና የተጠበቀ ነው ።

ለዚህ ውሳኔ ራብጠት አል ቅዱስ የምታርገው መልስ፣ ራብጠት አል ቅዱስ ምንም በቅብጦች ፍቅርና በቅዱስ ማርቆስ ሀገረ ስብከት ያላት ፍቅር ከፍ ያለ ቢሆን ፣ ነፃነቷን የሚነካ ውሸት ፣ ትግሏን የሚያቃልል ፣ ድካሟን የሚደመስስ ውሸት በዚህ ውሳኔ በትመለከት ልትቃወም በልሞከረች ነበር ። አሁን ራብጠት አል ቅዱስ የዚህን ውሳኔ መሳሳት ለመንካት አእምሮ በሚቀበለው አድርጋ ይህንን ቀጥሎ የተመለከተውን ትጽፋለች ።

አንደኛ ፣ በመጅሊስ ሚሊ ወኪል እንዲህ የሚል ውሳኔ ወጣ ፤ በዴር ሡልጣን ንብረት ጉዳይ የመጣው ጥል ጠቅላላውን የሕዝብ ሐሳብ አስደንግጧል ። ይህም ማለት በቅብጦች ንብረት በሚሆን የዴር ሡልጣንን ማለት ነው ። እንዲህ ራብጠት አል ቅዱስ በብዙ ዘመን ውስጥ ሕግ የሚመሰክርላቸውን ንብረት ማደስ ቅብጦች መሆን እንደሚገባቸው ለመከራከር ትነሣለች ። እንግዶቻችን ሐበሾች በውስጣችን ሲኖሩ እኛን አስተናጋጆቻቸውን ትተው ለማደስ ፣ ግድግዳንና መስኮትን ለመቅበት የጆርዳንን መንግሥት ቢለምኑ ልመናቸውን ተቀብሎ ሥራው በ፲፱፻፶፰ ዓ. ም. በመስከረም ወር ተጀምሮ እየተስፋፋ ሄደ ። መስኮቶች እየበዙ ሄደው ወደ ስልሳ ደርሰዋል ፤ ፰-፱ የነበረው፣

፴-፵ና ፵-፶ ሁኗል ። እንደዚሁም ፻፷-፻፸ የሚሆን አዲስ መስኮት ተከፍቷል ፣ የዮርዳኖስም መንግሥት አኳኋኑን አስለክቶ ለማደሻ ፻፹፫ ፓውንድ አጥፍቷል ።

፻፷-፻፸ የወጣውን መስኮት የወጣበትን እንዲት ኢትዮጵያዊት ልዕልት ትኖርበታለች ፣ እንደዚሁም አዳዲስ የበርና የመስኮት ዕንጨቶች ተበጅተው በአንድ ዓይነት ቀለም ተቀብተዋል ፣ ከጥቂቶች በቀር አብዛኛው አሁን ታድሶ ይገኛል ። አሁን ከባለ ቤቶች ይልቅ የእንግዶች መኖሪያ ቤቶች ታድሰው ይታያሉ ፤ ይህም የሆነው የመነኮሳት ኤጲስቆጶስ በሚሆኑት በአቡነ ፊልጶስ እስታቱስኮን በመተላለፍ ነው ።

አሁን ድምፃችንን የምናሰማው የመጅሊስ መቅደስ እንዲሁም በጳጳሳትና በኤጲስ ቆጶሳት የተወሰነ ውሳኔ ብፁዕ የሐበሻው ጳጳስ ፣ ኤጲስ ቆጶሳትን በሀገራቸው በሐበሻ ብቻ እንዲሾሙ እንጂ በሌላው እንዳይሾሙ ሕግን በማስታወስ ነው ። እንዲሁም ፴፫ኛውን የሐዋርያትን ሕግ በመጥቀስ ነው ። እርሱም ይህ ነው፤ ኤጲስ ቆጶስ በሀገረ ስብከቱ በስተቀር ከዚያ ውጭ ሊሾሙ አይገባም ፣ ይህንን ግን ከአስፈላጊው ጠብቆ ፈቃድ ሳይወስድ ያደረገ እንደሆን እርሱና ተሿሚው ይለዩ (ይወገዙ) ። ስለዚህ ፓትርያርኩ ለብፁዕ የሐበሻ ጳጳስ ወደ ውጭ እንዲሾም ያለ መጅሊሱ ፈቃድ አይሆንም ። እንግዲህ አስፈላጊው የኢየሩሳሌም አዛዥ የቀብጡ ጳጳስ መሆኑ ነው ። ራብጠት አል ቅዱስ በጽሑፍ መጅሊስ መቅደስን በ፲፱፻፷፫ ዓ. ም. ቢጠየቅ የሰብሰባው ጸሐፊ እውነትም ይህ ነገር እንግዳ ነው ፣ ሆኖም ለወደፊት አይለመድም ሲል መልስ ሰጠ ። ይህም የሆነው የሐበሻው ጳጳስ ለገዳሙና ለመነኮሳቱ የሚሆነውን ኤጲስ ቆጶስ ለመሾም ስለጠየቀ ነው እንጂ ጠባቂ ኤጲስ ቆጶስ አይደለም አለ ፣ ይኸውም የቤተ ክርስቲያን ሕግ እንደሚያዘው በፓትርያርክ ፈቃድ ጳጳስ ኤጲስ ቆጶስን ሲሾም ፣ ኤጲስ ቆጶሱ ዲያቆናትን ብቻ እንጂ ካህናት ሊሾም ሥልጣን የለውም ።

በጣም አስደናቂው አቡነ ፊልጶስ በጋዜጣ የሐበሾች ጳጳስ ብለው ስለ ራሳቸው ማውጣታቸው ነው ። እንደዚሁም በሐበሾች ገዳም በራፍ ላይ የሐበሾች ፓትርያርክ ግቢ ብለው ጽፈዋል ፣ ይህም ልታይ በማለት ከቅድስና መራቅ ነው ።

ሁለተኛ ፣ የራብጠት አል ቅዱስ አባሎች ከሊባኖስ ወደ ካይሮ በሚመለሱበት ጊዜ በሐበሾች ገዳም ውስጥ ትልቅ ግንብ መገንባቱን ተረድተው ለመጅሊሱ ይህንኑ ለማመልከት ወደ ፓትርያርኬቱ ሄደው ነበር ። ይህንንም በመስከረም ፳፫ ፣ ፲፱፻፸፮ ዓ.ም. ሊያቀርቡ በሄዱበት ጊዜ ሦስት የሐበሾች መነኮሳት በበትረከናው አርፈው ነበር ። በዚህም ጊዜ ፣ በኢየሩሳሌም ስለሚደረገው አባ ብንያምን ጠየቃቸው ። እነርሱም በእውነተኛነት አሥር መስኮቶች አስፍተን ፳፫ የነበረውን ፯ አድርገነዋል ሲሉ መሰከሩ ። ይህም የሆነው ቆሞስ ዳውድና ቆሞስ ሸኖዳ በፓትርያርኩ ግቢ በተገኙበት ጊዜ ነው ።

ሦስተኛ፣ የፓትርያርኩ መጅሊስ ይህንን ከተባሉት መነኮሳት ከተረዳ በኋላ፣ ይህ በእስታቱስኮና በቅብጦች ገንዘብ ላይ መተላለፍ እንደሆነ አውቆ በነገሩ ተጠንቅቆ ለአማን መንግሥት፣ ለአገር ግዛት ሚኒስቴር፣ ለውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ለአገረ ገዥውና እንዲሁም ለክቡር የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ይህንን መተላለፍ አስታወቀ። ለነዚህ ለተባሉት ራብጠት አል ቅዱስ ደብዳቤን ጻፈች ። እንደዚሁ የፓትርኬቱ መጅሊስ በአማን ለሚገኘው የግብጽ አም

በሳደርና ለአገረ ገዥው ቀጥሎ ያለውን ጻፈ፡ "አሁን በመጨረሻው ረግቶ በነበረው ይህ ንን ገዳም በመገንበት ብዙ ለውጥ ተደረገ፡ ይኸውም የክፍሎችን መስኮቶች በማስፋትና በሌላም ለውጭ የእስታቱስኮን ሕግ ተቃውሟል ።

አራተኛ ፡ ይህ ደብዳቤ በኢየሩሳሌምና በአማን ደርሶ በነበረበት ጊዜ አቡነ ማርቆስ አል አንጦኒ ለፖሊስ ክስ አቅርበው ሦስት አዲስ መስኮቶች በመከፈታቸው አስረዳ ።

አምስተኛ ፡ በአማን ያለው የግብጽ አምባሳደር ለካይሮ ፓትርያርኬት እንዲህ ሲል ጻፈ "የሥራ ክፍል ሠራተኛ በዴር ኤል ሱልጣን መስኮቶችና ሌሎችን ክፍሎች ማደስ ጀምሯል ። አባ እንጦንዮስም ሐበሾች መስኮትን እንዳስፋፉ አይቶ ይህንኑ ለማዘጋጃ ቤት በቴሌፎን አስታውቋል" ።

ስድስተኛ ፡ መጅሊስ ሚሊ እንደራሴዎች ወደ ኢየሩሳሌም ላከ ፤ ይህም እንደራሴ በደረሰ ጊዜ የማዘጋጃ ቤት ሹምንና ቅዱስ በታውን ተጠባባቂውን ተገናኛቸው ። በዚህም ጊዜ ይህ እንደራሴ ስለ ቀብጦች መብት ተከራክሮ እስታቱስኮ እንዳልተፈጸመና እንዳልተሠራበት ነገረ ። ከዚህ በኋላ ወደ ካይሮ ተመልሶ ከጳጳሳቱ ይህ ጽሑፍ ተላከ ፡ "በተሠራው ሥራ ሁሉ እስታቱስኮ እንዳልተሠራበት በጠቅላላው እናመለክታለን ። እስታቱስኮ ምንም ለውጥ ወይም ማደስ እንዳይደረግ ይከለክላል ። አሁንም ነገሩ እንዲጠብቅና እንዳለ እንዲሆን እንጠይቃለን" ።

ሰባተኛ ፡ አባ እንጦንዮስ የመንግሥቱን መሐንዲስ የረዳውን ዳውድ የሚባለውን ሰው በተላኩት ወኪሎች ፊት አቅርቦ የመስኮቶቹ መለዋወጥና አሮጌዎች መቃጠላቸውን አስመሰከረ ።

## የ በ ዓ ል   ወ ሬ ።

፩ በ፰፭-፱-፶፯ ዓ. ም. የጋዛና የኢየሩሌም ጳጳስ የሆኑት አቡነ ዮሐንስ በትምህርት መጀመርያ ቀን ለመገናኘት ወደ ኢየሩሳሌም ሂደዋል ። እንደዚሁም የቀብጦች መሬት በሚሆነው በዴር ሱልጣን ሜዳ ላይ ሐበሾች የብፁዕነታቸውን ፈቃድ ጠይቀው የመስቀል በዓልን በሚያሳዩበት ጊዜ ፈቅደው በዓሉን ይመለከታሉ ።

፪ የጋዛና የኢየሩሳሌም ጳጳስ ብጹዕ አቡነ ዮሐንስ ፡ ዴር ሱልጣን እንዲታደስ ፶፰፭ ፓውንድ ያወጣቸውን የዮርዳኖስን መንግሥት ለመክፈል ጠይቀዋል ። እስከሁን መንግሥቱ ለዚሁ መልስ አልሰጠም ። ጳጳሱም ይህ ገንዘብ በሕግ እንዲከፈል ለማድረግ ይፋጠናሉ ።

ጋዜጊ ፡ "የቀብጥ አርቶዶክስ ራብጠት አል ቅዱስ" ።

ኃምሳ ሁለተኛው ቍጥር
እ. ኤ. አ. ፲፱፻፶፯ ዓ. ም. ጥቅምት ፡
ሙሉጌታ መልክ ጼዴቅ ።

## የሥራ መግለጫ ሪፖርት ፣

### ለብፁዕ ወቅዱስ ፓትርያርክ ወርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ አበታችን አቡነ ባስልዮስ ፤

ብፁዕ ወቅዱስ ሆይ ፤

የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ከግብጾች ጋር ያላት መንፈሳዊ ግኑኝነት እጅግ የጐዳት (ያጠቃት) መሆኑ ግልጽ ነው ፡ ምክንያቱም በመላ ኢትዮጵያ መንፈሳዊ መብትን የግላቸው አድርገው ይዘው ፥ በራሷ ሥልጣን እንዳታስተምር አድርገው ጨቍነው ዛሬ እንሆ አገራችን ኢትዮጵያ በአእላፍ ሚስዮንና በእስላም ተከበ ትገኛለች ፤ ስለሆነ ግን ይህን ሰፊውን አስተያየት ለብፁዕነትዎ ትቼ በኢየሩሳሌም በቅዱሳት መከናት በሚገኘው በኢትዮጵያ ማኅበራችን ላይም የግብጾች አዋቂነትና ተጋፊነት ከጥንት ጀምሮ እስከ አሁን ጊዜያችንም ግፉ እንደቀጠለ መኖሩን አስረዳለሁ ።

፩ - ዴር ሥልጣን የሚባለው ገዳም ከጎልጎታ ቤተ ክርስቲያን ተያይዞ በምሥራቃዊ ክፍል የሚገኘው ገዳም ዛሬ የኮፕቶች ንብረት ሆኖ እስከሚታየው ስፍራ ሳይቀር በመላው የኢትዮጵያ ርስት እንደነበረ ማስረጃው ይነግረናል ፥ ነገር ግን፥ ኮፕቶች አሁን እነሱ ያሉበትን የዴር ሡልጣን ክፍል ተደላድለው እጅ ከደረጉ በኋላም ፥ ዛሬ ከኛው እጅ ያልወጣውንም ከዴር ሥልጣን አንድ ክፍል የሆነውን ገዳማችንን የኮፕቶች ርስት ነው ፥ በውስጡ ስፍራው የሚገኙት የሐበሻ መነኮሳትም እኛው በእንግድነት ተቀብለን ያስቀመጥናቸው እንግዶቻችን ናቸው ይላሉ ።

እንደዚህ ለማለት የረዳቸው ከላይ በመነሻው እንደገለጽኩት የኢትዮጵያን መንፈሳዊ ሥልጣን በመውሰዳቸው ምክንያት የኢትዮጵያ መነኮሳት ወደ ዳኛ በቀረቡ ቍጥር እነዚህ የኛ ጥገኞች ናቸው፥ እንኳንስ በዚህ በውጭ አገርና በገራቸውም የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን በመላዋ የምትተዳደር በኛ በኮፕቶች ሥልጣን ሥር ነው ። ለነዚህም አሳዳሪያቸው እኛ ነን እያሉ ነገራቸው እንዳይደመጥ አድርገው ኢትዮጵያውንን ጨቍነው በርስታችን ሠልጥነውበት የኖሩት ስለዚህ ነው ።

፪ - ይህንን የኢትዮጵያውያንን ገዳም በኢትዮጵያዊ ጳጳስ ሥልጣን ሥር እንዲተዳደር ሆኖ በልዑል እግዚአብሔር ፈቃድ በግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ መልክም አስተያየት በቅዱስነትዎ ሽዋሚነት እኔ ተልኬ ኢየሩሳሌም ከገባሁበት ጊዜ ጀምሮም ኮፕቶች ይኸው አሮጌ ልማዳቸውን በመቀጠል በገንዘብ፥ በተንኮል ሥራ፥ ጋዜጣን በመጻፍ፥ የምሥርን መንግሥት ድጋፍ በማድረግ፥ ይኸውና በልዩ ልዩ አኳኋን በለ ኃይላቸው እውነቱን በሐሰት ለማሸነፍ ሲታገሉ ይገኛሉ ።

ይሁን እንጅ በ፲፱፻፵፩ ዓ. ም. ብፁዕነትዎ ለቅዱስ ማርቆስ ቤተ ክርስቲያን ሁራኬ ካይሮ በተገኙበት ጊዜ በእስክንድርያ ፓትርያርክ በብፁዕ አቡነ ዮሳብ ፈቃድ በኢትዮጵያና በግብጾች መካከል ያለውን የዴር ሥልጣንን ገዳም ክርክር በስምምነት ለመጨረስ ታስበ በተደረገው ኮሚስዮን መካከል የኮፕቶች ጳጳስ የነበረው አባ ያዕቆብ በኢትዮጵያውያን ላይ የተናገረውን የንቀትና የተግዳሮት ንግግር ፥ በማግሥቱም ኮፕቶች በዓ

ረብ ጋዜጣ የጻፉብንን ክብርን የሚነካ አስቀያሚ ቃል ከሰሙ በኋላ ብፁዕነትዎ ከእንግዲህ ወዲህ ለዚህ ነገር ምንም ብታደርግ በኮፕቶች በኩል ቅርታ የለኝም ፣ እግዚአብሔር ይርዳህ ሲሉ መርቀው ለዚህ ሥራ መከላከያ ይሁንህ ብለው ልዩ ወጭ ከላኩልኝ በኋላ የተፈጸመውን የሥራውን ፍሬ እንደሚከተለው እዘረዝራለሁ ።

፩ኛ ፣ ኮፕቶች ከላይ እንደተነገረው በበላይነት ሥልጣን የገዳማችንን መብት ይዘው ቤቶቹ ቢፈርሱ እንዳይጠገኑ ፣ ዝናም ቢያፈሱ እንዳይታደሱ ፣ ቢቈሽሹ እንዳይጸዱ አድርገው የማደሱ መብት የኛ ነው ፣ ማንም አይገባበትም እያሉ ከልክለው የቤቶቹን መፍረስና የገዳሙም ቆሻሽነትና አስቀያሚነት ለተመልካች ሁሉ አስቀይሞ የነበረውን ለማሳደስ እንድንችል ።

፪ኛ ፣ ለትንሣኤና ለመስቀል ዓበይት በዓላት በምናከብርበት መላው ዓለም የኢትዮጵያን ስነ በዓል ለመመልከት በሚሰበሰብበት ጊዜም፣ የግብጹ ጳጳስ ርስቱ መብቱ የኔ ነው ፣ እኔን ለምነው ካልሆነ በስተቀር በሩም አልከፍትም እያለ በዓላችንን ሰው እንዳይመለከተው በደምብ እንዳይከበር በዓሉ ይታጐል የነበረውን ለግብጹ ጳጳስ በኛ ላይ ይህን ያህል መብት የለውም፣ በሩም በጥንታዊው ሕግ በደምብ ይከፈታል እንጂ ኢትዮጵያ መብት የሌለው ግብጹን ባለመብት አድርጋ የግብጹን ጳጳስ ክፈትልን ብለን መለመን የለብንም ብዬ ጠበቃ ገዝቼ በሕግ መሠረት ለጆርዳን መንግሥት ማመልከቻ አቅርቤ እውነተኛ ፍርድ ጠይቀን የጆርዳን መንግሥትም ያቀረብነውን ማመልከቻና የኮፕቶችን መልስ መርምሮ ከተረዳ በኋላ ፣

ሀ ) የነዚህ የሁለቱ ጠበኞች የኢትዮጵያና ግብጾች ክርክር በፍርድ አልቆ ባለመብቱ እስኪወሰን ድረስ ገዳሙን መንግሥት ያድሰዋል እንጂ ይህ ነገር በፍርድ ከማለቁ በፊት ሁለቱም ወገኖች ገዳሙን ለማደስ መብት የላቸውም ፣ መንግሥት ገዳሙን በማደስና በማጽዳት የሰውን ሕይወት ይጠብቃል ።

ለ ) ኢትዮጵያውያን የተለመደውን የመስቀልና የትንሣኤን በዓላት በሌሊት ሲያከብሩ በሩ በሕግ ይከፈትላቸዋል እንጂ ኮፕቶችን መጠየቅ (ክፈቱልን ብሎ መለመን) የለባቸውም ።

ሐ ) ኢትዮጵያን ከጥንት ሲያያዝ የቆየውን የሃይማኖት አገልግሎታቸውን ማንም ሳይቃወማቸው መፈጸም ይችላሉ ሲል በኮሚስዮን ወስኖ ለሁለታችን ጠበኞች የሰጠንን መልካምና ትክክለኛው ብያኔውን በፎቶግራፍ አስነሥቼ ለቅዱስነትዎ ከሁን ቀደም የላኩት ማስረጃ በመዝገብ ቤትዎ ይገኛል ።

መ ) በዚህ ብያኔ መሠረት የጆርዳን መንግሥት የሥራ ሚኒስቴሩን አዝዞ በጣም ተበላሽቶና ወድቆ የነበረው ገዳማችንን የጥንት ሥራውን ሳይለቅ የድንጋይ ሥራ የነበረውን አዲስ ጥርብ ድንጋይ እያገባ በሲሚንቶ ሥራ የነበረውን፣ አዲስ ሲሚንቶ አሸዋ እያገባ ፣ በፅንጨትና በቆርቆሮ የነበረውን አዲስ ፅንጨትና አዲስ ቆርቆሮ እየገዛ አግብቶ ደህና አድርጎ ሠርቶታል ።

ሠ ) የገዳሙም ምድረ ግቢ እንደሚያውቁት የድንጋይ ጕራንጕርና የቆሻሻ መጣያ የነበረውን ምድረ ግቢውን፣ በሙሉ በሲሚንቶና በጠጠር ቤቱን አንጥፎ መንገዱንም ሁሉ በደምብ ሠርተው ግቢው ሁሉ የአስፋልት መንገድ መስሎ ተሠርቶ ይገኛል፣ በዴር አብርሃምና በመስኮቦች መካከል ወደ ገዳማችን በኩል ተንጠልጥሎ ድንጋይ እየወደቀ ሰውነታችንን ያሰጋ የነበረው የጥንቱን አሮጌውን ግንብ ፣ በሲሚንቶ አድርገው በሚገባ ተሠርቶ ይገኛል ።

ሬ ) የሚበቃ ብርሃን የሚሰጥ መስኮት ያልነበራቸውንም ቤቶች፣ ጠባብ የነበረውን እያሰፋ፣ ያልነበረውም መስኮት አዲስ እያወጣ በደምብ ሆኖ ተሠርቶ ይገኛል ።

ይኸውም ሥራ ካፕቶችን አለመጠን አስቀይሚያቸው ከኛ መኖሪያ የእንግዶቻችን መኖሪያ የበለጠ ሆኖ ተሠራ በማለት ያቀረቡት አቤቱታና በኛ ገዳም የተፈጸመውን የሥራ ዝርዝር በመግለጽ የግብጹን ሕዝበ ክርስቲያን በመላው በኛ ላይ ለማስነሣት የጻፉት ጋዜጣ በማርኛ አስተርጒሜ ብፁዕነትዎ ይመለከቱልኝ ዘንድና ወደፊትም ግብጾች ያላረፉልን መሆናቸውን በመግለጽ፣የካቲት ፳፩ ቀን ፲፱፻፶ ዓ. ም. በቁጥር ፺፬ ማመልከቻና አባሬ አድርጌ የላክሁት የጋዜጣው ግልባጭ በመዝገብ ቤትዎ የሚገኝ መሆኑን በማስረዳት ይመለከቱልኝ ዘንድ አሁንም አሳስባለሁ፤ የኮፕቶቹ ጋዜጣ እኔን ሾመው በመላክዎ ምክንያት አድርጎ የብፁዕነትዎንም ክብር ይነካል ።

ብፁዕ ወቅዱስ ፓትርያርክ ሆይ፤

ይህ ሁሉ የሥራ ዝርዝር ሊፈጸም የተቻለው ሥራበት ያውልህ ብለው በሰጡኝ ገንዘብ ኃይል መሆኑን እገልጻለሁ ።

ብፁዕ ወቅዱስ አባታችን ሆይ፤

ከዚህ በላይ በቅድስናዎ እርዳታ የተፈጸመውን ገለጽሁ እንጂ፣ ነገሩ በዚህ ብቻ የተወሰነ አይደለም ። ኮፕቶች እስታቱስኮ የተባለውን ሕግ ተላልፈው ከሕጉ ውሳኔ በኋላ የገዳማችንን መክፈቻ ወስደው ሁለቱን ቤተ ክርስቲያኖቻችን አርባዕቱ እንስሳና ቅዱስ ሚካኤልን ከጥንት ጀምሮ የሃይማኖት አገልግሎት እንፈጽምባቸው የነበረውን ያለ ፍርድ በራሳቸው ሥልጣን ብቻ በግፍ ዘግተውብን ስለሚገኙ ፣ ይህ ተግባር ከሕግ ውጭ በግፍ የተሠራብን ነውና ፣ በዓለም መንግሥታት ታውቆ ከተወሰነው ሕግ (ከእስታቱስኮ) በኋላ ሕጉን ተላልፈው ኮፕቶች የወሰዱብን የገዳማችን መክፈቻ ለኛ ለባለቤቶቹ ይመለሳል ። በግፍ የተዘጉ ቤተ ክርስቲያኖቻችንም ለኛ ለባለ ንብረቶች ተለቀው እንድንቀድስበቸው ሆነው ኮፕቶችም ይህን ቅዱስን መቅደስ መመላለሻ ጒዳና ከማድረግ እንዲከለከሉ ይፈረድባቸዋል ። ስንል ፣ አዲስ ክስ አቅርበን ፣ ቅን ፍርድን በመጠባበቅ እንገኛለን ።

ይህም ሲሆን ፣ ያለንን ማስረጃ ሁሉ ሰብስበን ከነ ክልሼው ጭምር አዘጋጅተን በዓረብኛና በእንግሊዝኛ አጽፈን ለተሰጠን ፈራጅ ያቀረብነው መጽሐፍ ለማዘጋጀት የተቻለው በላይኛው መሥመር በተገለጸው ብፁዕነትዎ በሰጡኝ ገንዘብ ኃይል እርዳታ መሆኑን አስረዳለሁ ።

ብፁዕ ወቅዱስ ፓትርያርክ አባታችን ሆይ ፣

ወደ ፊትም በጸሎትዎ ይፈጸምልናል ብለን የቀጠልነው የኮፕቶች ተጋድሎ እንሱም በጻፉት ጋዜጣ እንደገለጹት ፣ እንደዚሁ በቀላል የሚያልቅ አለመሆኑን ግልጽ ነውና ፣ የተለመደው እርዳታዎንና ጸሎትዎን ሳያቋርጡ እስከ ፍጻሜው ይረዱን ዘንድ በማሳሰብ ንግግሬን አቆማለሁ ።

ዕድሜ ለግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ፤
ዕድሜ ለቅድስናዎ ፤

ታዛዥዎ አባ ፊልጶስ ።